# ክፍል ፩

# ጥቁር ዳመና
# በኢትዮጵያ ፀሐይ

# ምዕራፍ ፩

## የአድዋን ብድር መመለስ አለብን !

### የሙሶሊኒ ዝግጅት 1933 - 1935 ( እ.ኤ.አ.)

ቤኒቶ ሙሶሊኒ የአሥራ ሦስት ዓመት ልጅ በነበረ ጊዜ፣ ኮሎኒያሊስት ጣልያን አድዋ ላይ በምኒልክ ጦር ድል ሆና ከፍተኛ ውርደት የደረሰባት መሆንዋን ሲሰማ፣ « ... **ይህንን ብድር የኛ ትውልድ መመለስና የአገራችንን ታሪክ ማደስ አለብን** ... » ብሎ ነበር እየተባለ በአፈ ታሪክ ሲነገርለት ቆይቷል። ቤኒቶ፣ ይህን ተናግሮ ነበር ተብሎ ከተወራ፣ ከሠላሳ ስምንት (38) ዓመታት በኋላ፣ ቀጥሎም ጣልያንን በሙሉ ሥልጣን ከያዘ ከአሥራ ሁለት (12) ዓመታት በኋላ፣ ኢትዮጵያን በጦር ኃይል ወግቶ የአድዋን ብድር ለመመለስና አገሪቱን ቅኝ ግዛቱ ለማድረግ ወሰኖ ተነሣ።

ሙሶሊኒ በኢትዮጵያ ላይ ጦርነቱን በይፋ ከመክፈቱ አስቀድሞ ዝግጅቱን የጀመረው ከሦስት ዓመት በፊት ነበር። እ.ኤ.አ በ1932 ዓ.ም በፋሽስቱ መንግሥት ካቢኔ ውስጥ የቅኝ ግዛቶች ጉዳይ ሚኒስትር የነበረው ጄኔራል ደ-ቦኖ (De-Bono) በምሥጢር ወደ ኤርትራና ሱማሌ ሄዶ፣ የኢትዮጵያን ግዛት በሰሜንና በደቡብ በኩል በጦር ለመውረር ስለሚቻልበት ጉዳይ እንዲያጠና ተደረገ። ጄኔራል ደ-ቦኖ ከተላከበት ሚሲዮን ሲመለስ፣ « ... **የገንዘብ ችግር ካልገጠመን በስተቀር፣ ዘመናዊ ጦራችንን በሚገባ አዘጋጅተን ኢትዮጵያን ለመያዝ የሚወስድብን ጊዜ በጣም አጭር ይሆናል** ... » ሲል ዱቼን የሚያስደስት ራፖር አቀረበ። ለዚህ ዓላማ የገንዘብ ችግር አለመኖሩን ሙሶሊኒ ሲያረጋግጥለት፣ ጄኔራሉ ወደዚያው ይቀጥልና ዕድሜህ ገፍቷል ካልተባልኩ በስተቀር፣ ወደ ኢትዮጵያ ለሚዘምተው ጦር፣ የአዛዥነቱ ክብር ለእኔ ቢሰጠኝ፣ የአገልግሎት ታሪኬን በመልካም ፈጽሚያለሁ ብዬ ለመደሰት እችል ነበር ብሎ አመለከተ። በዚያች ሰዓት ሙሶሊኒ በጥሩ መንፈስ ላይ ይገኝ ስለነበረ፣ ወደ ኢትዮጵያ ለሚዘምተው ጦር ደ-ቦኖ እንዳመለከተው፣ ዋና አዛዥ እንደሚሆን ካረጋገጠለት በኋላ፣ « ... **ከዛሬ ጀምሮ አንድም ቀን በከንቱ ማለፍ የለበትም። በኤርትራና በሱማሌ ግዛታችን በኩል የአየር፣ የየብስና የባሕር መገናኛዎቻችንን ለማመቻቸት፣ ጦራችንን በሚገባ ለማዘጋጀት፣ አስፈላጊውን ሁሉ በምሥጢር እንድታከናውን ኃላፊነቱን ሰጥቼሃለሁ** ... » ብሎ ያሰናበተው።

ኤሚሊዮ ደ-ቦኖ በታሪክ ማስታወሻው ላይ እንደገለጠው፣ የሙሶሊኒ ዕቅድና ምኞት፣ እ.ኤ.አ ከ1936 ዓ.ም ፍጻሜ በፊት ኢትዮጵያን በሙሉ ለመያዝ ስለሆነ፣ ለዘመቻው የሚያስፈልገውን ትጥቅና የጦሩን ፕላን ስናዘጋጅ፣ ዱቼ ሌሊትም ሆነ ቀን እቢሮውም ሆነ እቤቱ እየጠራን በብርቱ ይቆጣጠረን ነበር ብሏል። በዱቼ ትእዛዝ፣ ኢትዮጵያን ለመውጋት የሚዘጋጀው የፋሽስት የጦር ኃይል በጠቅላላው ከሦስት መቶ እስከ አምስት መቶ ሺህ የሚደርሱትን ተዋጊ ወታደሮችን በዘመናዊ መሣሪያ ለማስታጠቅ ሲሆን፣ ቁጥራቸው ከሁለት መቶ እስከ አምስት መቶ የሚሆኑ የአየር ኃይል ቦንብ ጣይ አውሮፕላኖችን፣ በብዙ ሺህ የሚቆጠሩ ታንኮችንና ታላላቅ መድፎችን፣ በአገሩ ውስጥ ያሉት የጦር መሣሪያ ኢንዱስትሪዎች በሙሉ፣ ሌት ተቀን እየሠሩ አንድ ዓመት ባልሞላ ጊዜ ውስጥ እንዲያጠናቅቁ ተወሰነ። **ጦሩ በሁለት አቅጣጫ ተከፍሎ፣ የመጀመሪያው በከፍተኛ ደረጃ የሚዘጋጀው በሰሜን ኢትዮጵያ በኤርትራ ግዛት ላይ ሲሆን፣ በሁለተኛ ደረጃ የሚሰናዳው ደግሞ በደቡብ ኢትዮጵያ በሱማሌ በኩል እንዲሆን ተደረገ።**



ኢትዮጵያ ያደረሰችብንን የአድዋን ብድር፤ እጅግ አስደናቂ በሆነ ድል ለመመለስ ለጣልያን ሕዝብ ቃል እገባለሁ።።

ቤኒቶ ሙሶሊኒ (Oct.1935)

እንግዲህ! የፋሽስት ጦር ዝግጅትና ድልድል ከዚህ በላይ በተገለጸው አኳኋን እየተፋፋመ ሲሄድ፤ በፕሮፓጋንዳ በኩል ደግሞ በሦስት ደረጃዎች ተከፍለው የሚያጠቁ የተለያዩ ፕሮግራሞች ተዘረጉ። እነዚህም፦

1ኛ/ በኢትዮጵያና በጣልያን ቅኝ ግዛት ወሰን ላይ፤ የፋሽስት መንግሥት አንድ ሰበብ ፈጥሮ ግጭት በሚደረግበት ጊዜ፤ ጠቡን የጫረችውና ጦርነቱን የከፈተችው ኢትዮጵያ መሆንዋን ለመንግሥታት ማህበርና ለዓለም ሕዝብ ማስረዳት፤

2ኛ/ ኢትዮጵያ፤ ከአሥራ አንድ ዓመታት በፊት፤ የመንግሥታት ማህበር አባል ስትሆን፤ የአገሬን አስተዳደር በአስቸኳይ በመለወጥ አሻሽላለሁ ብላ የሰጠችውን ቃል ባለማክበሯ፤ ከሊግ ኦፍ ኔሽን እንድትባረር ክስ ማቅረብ፤

3ኛ/ በሁለቱ አገሮች ወሰን ላይ ሆነ ተብሎ በዘዴ የሚፈጠረው ጠብ እየከረረ ሲሄድ፤ የፋሽስት መንግሥት በቅኝ የሚያስተዳድራቸውን ሕዝቦች ሰላምና ደህንነት ለመጠበቅ ባለው ኃላፊነት፤ ወራሪ ሆነችውን ኢትዮጵያን በጦር ወግቶ ለመያዝ የተገደደ መሆኑን የዓለም ሕዝብና የመንግሥታት ማህበር እንዲገነዘቡት ማድረግ፤

እነዚህ የተተለሙት የፕሮፓጋንዳ መሣሪያዎች ሁሉ፤ የዓለምን ሕዝብ አስተያየት ከዱቼ ሙሶሊኒ ጋር የሚያስተባብሩ ይሆናሉ ተብለው ከፍ ያለ ተስፋ ተደረገባቸው።

ከዚህ በላይ የተገለጹት የፕሮፓጋንዳ ዝግጅቶች የሚሠራጩት፤ ለመንግሥታት ማህበርና ለዓለም ሕዝብ ሲሆን፤ በአገሩ ውስጥ ለጣልያኑ ተወላጅ ደግሞ ሙሶሊኒ ራሱ በየሥፍራው እየተዘዋወረ የሚያደርጋቸው ዲስኩሮችና የሚሰጣቸው መግለጫዎች በተለየ አቀራረብ ነበር። ሙሶሊኒ፤ በየአደባባዩ እየደነፋ ከሚናገራቸው ዲስኩሮች ዋና ዋናዎቹም የሚከተሉት ነበሩ።

1ኛ/ እ.ኤ.አ በ1896 ዓ.ም፤ አገራችንን ይመራ የነበረው የክሪስፒ መንግሥት ባደረገው ይቅርታ የማይደረግለት ጥፋት፤ ኢትዮጵያ የምትባል አንዲት ያልሠለጠነችና በጭለማው ዓለም ውስጥ የምትዋኝ የጥቁር ሕዝብ አገር፤ " አድዋ " ከሚባለው ግዛቷ ላይ ጣልያንን የሚያህል ትልቅ አገር፤ በጦርነት ገጥማ ድል አደረገች ተብሎ በታሪካችን ላይ የተቀበልነውን ውርደት ሁላችሁም ታስታውሳላችሁ። እኛ የዛሬዎቹ ጣልያኖች ይህንን ከዐርባ ዓመታት በፊት በታሪካችን ላይ የተለጠፈብንን ውርደት፤ ሳንደመስስና ብድሩን መልሰን በአዲስ የሚያኮራ ታሪክ ሳንተካ፤ እንቅልፍ ሊኖረን አይገባም።

2ኛ/ ዋናው ዓላማችን በክሪስፒ ዘመን የጐደፈብንን ታሪካችንን፤ ቀድሞ ወደ ነበረበት ወደ ተከበረው ቦታችን መመለስ ብቻ ሳይሆን፤ በዚች ኢትዮጵያ በምትባል በዕውር ዓለም ውስጥ በምትገኝ አገር ያሉትን፤ ሰፋፊ መሬቶችና ያልተነኩ ማዕድኖችን በማልማት፤ ብልጽግናው ለአገራችን ለጣልያን ሕዝብና በአፍሪካም ለሚገኙት ዜጐቻችን እንዲጠቅም ለማድረግ ነው።

3ኛ/ ይህች ፍጹም በሆነ በፊውዳል አስተዳደር የምትገኝ አገር፤ ኢኮኖሚዋ የተመሠረተው የሰውን ልጅ " ባርያ " እያለች በመሸጥ በምታካሂደው ንግድና፤ ከያለበት በኮንትሮባንድ የሚሰራጩ መሣሪያዎችን እየተቀበለች ሕገ

ወጥ በሆነ መንገድ ወደ ቅኝ ግዛቶቻችን በማሻገር በምታገኘው ገቢ ነው። ይህንን ስትሰሙ መገረም ብቻ ሳይሆን ምን ያህል እንደምታዝኑ አውቃለሁ። ... ይህች አገር ከጥንት ጀምሮ የጣልያንን መንግሥትና ሕዝብ የምትመለከተው በፍጹም ጠላትነት ስለሆነ፣ ጉረቤቶቿ በሆኑት በቅኝ ግዛቶቻችን በኤርትራና በሱማሌ ዜጐቻችን ላይ ወሰን እየጣሰች በየጊዜው የምታደርስብን ጉዳት ተዘርዝሮ አያልቅም። በዚህም ምክንያት የስንቶቹ ዜጐቻችን ሕይወት በከንቱ አልፏል። ... ይህን ሁሉ ስናገር ካዳመጣችሁኝ በኋላ፣ **እንግዲህ መሪያችን (ዱቼ) ምን እስኪደርስ ነው የሚታገሠው? ብላችሁ እንደምታስቡ እርግጠኛ ነኝ። እመኑኝ! ለጥያቄያችሁ መልሱን ሳላዘገይ አስታውቃችኋለሁ። እስከዚያው ዝግጅታችን ይቀጥላል።**

እንግዲህ ! ከዚህ በላይ በዝርዝር እንደ ተገለጸው፣ የሙሶሊኒ ዋና ዓላማ፣

1ኛ/ ኢትዮጵያን በጦር ወግቶ ድል ማድረግና የአድዋን ብድር መለስኩ በማለት፣ በጣልያን ሕዝብ ላይ ኩራት ለማሳደር፣

2ኛ/ ኢትዮጵያን ቅኝ ግዛቱ አድርጐ በመያዝ፣ በአገሩ ጥበት ምክንያት ተጨናንቆ ለሚኖረው የጣልያን ሕዝብ የመስፈሪያና ተመቻችቶ የሚኖርበት ዕድል ለመስጠት፣ መሆኑ ታውቋል።

ይህንኑም ዓላማውን ከግቡ ለማድረስ፣ ሙሶሊኒ የሚያዘጋጃቸው የጦር ኃይሎችና የፕሮፓጋንዳ መሣሪያዎች ከመጠን በላይ መሆናቸው ሲታይ፣ በውነት ኢትዮጵያን ለመሰለ ለአንድ ደሃ አገር፣ይህ ሁሉ ያስፈልግ ኖርዋል ወይ ? የሚል ጥያቄ ሊቀርብ ይችላል። ነገር ግን፣ ሙሶሊኒ ብዙ የሚፈራው ነገር ነበረው።

**ኢትዮጵያ እንደ ጣልያን፣** ከሦስት እስከ አምስት መቶ የሚደርሱ የአየር ኃይል ተዋጊ አውሮፕላኖች ይኖሯታል ተብሎ ባይጠረጠርም

**ኢትዮጵያ እንደ ጣልያን፣** ሥፍር ቁጥር የሌላቸው ታንኮችና ከፍተኛ መድፎች አግኝታ ለጦር ትሰለፋለች ተብሎ ባይጠበቅም፣

**ኢትዮጵያ እንደ ጣልያን፣** የብዙ መቶ ሺህ ወታደሮች ትጥቅና ስንቅ ለማዘጋጀት አቅም አላት ተብሎ ባይታሰብም፣

**ኢትዮጵያ እንደ ጣልያን፣** የዓለምን ሕዝብ አስተያየት በማወናበድ ድጋፍ የሚያስገኙ፣ የፕሮፓጋንዳ መሣሪያዎች ለማጥመድ ትችላለች ባይባልም፣

**ለነፃነቱ ደሙን ለማፍሰስ የሚቆርጥና እሳቱን ተጋፍጦ ጠላቱን የሚመክት ጀግና ሕዝብ ስለአላት፣ ኢትዮጵያን በቀላሉ ድል ለማድረግ እጅግ እንደሚያስቸግር፣ ሙሶሊኒ ተገንዝቦ ጭንቅና ፍርሃት አድሮበታል። ስለዚህ፣ ኮማንዳቶሬ ዱቼ፣ አገሩ ያለውን ሀብትና ገንዘብ አሰባስቦ ለዚህ ትልቅ የጦር ኃይል ዝግጅት ለማዋል ያሰበው፣ በጣልያን ታሪክ ውስጥ፣ ኢትዮጵያ የአድዋን ድል እንዳትደግምና የበለጠ እንዳታዋርድ ክፉኛ በመሥጋት ነው።**

# ምዕራፍ ፩

## ለእሳቱ መጫሪያ
## የወልወል ግጭት

እ.ኤ.አ ታህሣሥ 5 ቀን 1934 ዓ.ም ከእኩለ ቀን በኋላ በዘጠኝ ሰዓት ተኩል በኦጋዴን አውራጃ " ወልወል" በተባለው ቦታ ላይ፣ በኢትዮጵያ ፀጥታ አስከባሪዎችና በጣልያን ወታደሮች መካከል የደረሰው ግጭት፣ ሁለቱን አገሮች ወደ ጦርነት የመራ ምክንያት ነው እየተባለ፣ በየትኛውም የዓለም ታሪክ ላይ ሲጠቀስ የሚኖር ሆኗል። ነገር ግን የወልወል ግጭት ከደረሰ ከዐሥር ወራት በኋላ፣ በጥቅምት 1935 ዓ.ም በሁለቱ አገሮች መካከል የተነሣው ትልቁ ጦርነት፣ እውነተኛው ምክንያት ምን እንደሆነ በጥልቀት ከተጠና፣ የፋሽስት መንግሥት ኢትዮጵያን ወግቶ ቅኝ ግዛቱ ለማድረግ በተነሣ ጊዜ፣ **ይህ የወልወል ጠብ የጦርነቱ መከፈቻ ሰበብ እንዲሆንለት፣ ሙሶሊኒ ራሱ ያዘጋጀው ተንኮል መሆኑን በቀላሉ መረዳት ይቻላል።**

ከዚህ ቀደም ባለው ምዕራፍ ላይ እንደተገለጸው፣ ሙሶሊኒ ኢትዮጵያን ቅኝ ግዛቱ ለማድረግ ከወሰነ በኋላ፣ በጦር ኃይል እና በፕሮፖጋንዳ ረገድ የሚያስፈልጉትን ዝግጅቶች በፕላን ሲያስጠና፣ ከእነዚህ ውስጥ አንዱ፣ ጦርነቱን ለመክፈት ለዓለም ሕዝብ ምን ምክንያት መስጠት እንዳለበት፣ ሰበቡን መፍጠር ነበረበት። ፋሽስቶቹ ኤክስፐርቶች በዚህ ጉዳይ ላይ ሰፋ ያለ ጥናት ሲያደርጉ፣ **የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ፣ በምንም ምክንያት በጣልያን ላይ ጠብ ለመጫር እንኳንስ የሚሞክሩ የሚያስቡም እንዳልሆኑ፣ ሁሉም እርግጠኞች ሆኑ።** በሌላ በኩል ደግሞ የፋሽስቱ መንግሥት በዓለም ላይ ነፃነቷ የታወቀውን ኢትዮጵያን፣ ያለ አንዳች ምክንያት ብድግ ብሎ ለመውረር ጦርነት ቢከፍት፣ ብዙ ችግር ላይ እንደሚወድቅ የሁሉም ዕምነት ሆነ። ስለዚህ፣ የፋሽስት የጦር ኃይል የኢትዮጵያን ወሰን ጥሶ ጦርነቱን ለመጀመር፣ በዓለም ሕዝብ ዘንድ በመጠኑም ቢሆን ተቀባይነት ሊኖረው የሚችል አንድ ዓይነት ምክንያት መፍጠር ግዴታ መሆኑን ሁሉም ተስማሙበት። ለዚህም፣ የፋሽስት የጦርና የሲቪል ሹማምንት ተሰብስበው ሲያጠኑ፣ መልካም ዘዴ ሆኖ የታያቸው የሚከተለው ነበር።

ኢትዮጵያ፣ ወሰንተኞቿ ከሆኑት ከእንግሊዝ፣ ከፈረንሣይና ከጣልያን ቅኝ ግዛት አገሮች ጋር፣ በየጊዜው ችግር ሳትፈጥር በሰላም ያሳለፈችበት ዓመት ታይቶ አይታወቅም። ከምኒልክ ዘመን ጀምሮ በወሰናችን ላይ ኢትዮጵያ የምትሾማቸው ገዥዎችና ጠረፍ ጠባቂዎች፣ ወንበዴዎችን እያሰለጠኑ ወደየግዛታችን በማሻገር፣ የሚያስፈጽሙትን የዝርፊያና የግድያ ወንጀል ለማቆም እስከዛሬ የሚቻል አልሆነም። ይህን የመሳሰለው ችግር ምን ያህል ጊዜ እንደደረሰ፣ በተለይ የእንግሊዝና የፈረንሣይ መንግሥታት የሰበሰቧቸው መረጃዎች ብዙዎች ናቸው፡ ለምሳሌም ያህል አንድ ጊዜ፣ የእንግሊዝ መንግሥት ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር ዊልፍሬድ ቴሲገር (Wilfred Thesiger) በብርቱ ከመበሳጨቱ የተነሳ፣ " ... **ኢትዮጵያ በወሰኖቿ ላይ እየሾመች የምትመድባቸውን የወንበዴዎች ግብረአበሮች የሆኑትን**

ሰዎች፣ ለመቆጣጠርና ለመቅጣት ካልቻለች፣ ምኑን መንግሥት ነኝ ለማለት ትችላለች? ... " ሲል የተናገረው ምን ያህል መሠረታዊ ጉዳይ መሆኑን በትክክል አጉልቶ ያመለክታል። ስለዚህም፣ እንግሊዝ፣ ፈረንሣይና ጣልያን የዜጐቻቸው ሰላም እየደፈረሰና የውንብድና ወንጀል እየተፈጸመባቸው መኖር ስለማይችሉ፣ ሦስቱም ተባብረው በኢትዮጵያ ላይ አንድ ዓይነት እርምጃ መውሰድ እንደሚገባቸው ለማንም ግልጽ ነው። አሁን ግን ፋሽስቷ ጣልያን፣ በዚህም ሆነ በሌሎች ጉዳዮች፣ ኢትዮጵያ የምታደርስባት በደልና ጥቃት ብዙዎች በመሆናቸው ትዕግሥቷ ስለአለቀ፣ በዚች አገር ላይ ለምትወስደው እርምጃ መነሻ የሚሆናት፣ የተለመደው በየጊዜው በወሰን ላይ ከሚደርሰው ችግር፣ ሌላ የተሻለ ምክንያት ሊገኝ አልቻለም።

የኢትዮጵያ መንግሥት የጠረፍ ጥበቃ ባለሥልጣኖች ከዚህ ቀደም በእንግሊዞች ላይ እንደ አደረጉት ሁሉ፣ በእኛም ወሰን ላይ አንድ አደጋ ጥለው ዕድሉን እስከሚሰጡን ጊዜ ከመፍጀት፣ እኛው ራሳችን ጠቡን ፈጥረን ምክንያታችንን በማጠናከር፣ ግባችንን መምታት የሚበጅ ሆኖ አግኝተነዋል። ይኸውም፣ የሁለቱ አገሮቻችንን ግዛት በሚያዋስን ምቹ ቦታ ላይ፣ የጦር ኃይላችንን በሚገባ አዘጋጅተን፣ የኢትዮጵያን የጠረፍ ጠባቂ ወታደሮች በመተንኮስ ውጊያ ሲደረግና የሰዎች ሕይወት ሲያልፍ፣ አጥቂዎቹ ኢትዮጵያውያኖች፣ ተጠቂዎቹ ጣልያኖች መሆናቸውን በፕሮፖጋንዳ ዘመቻ ለዓለም በማሳወቅ፣ የብዙዎች መንግሥታትን የድጋፍ አስተያየት የማግኘት ዕድል ይኖረናል። ጓደኞቻችን የእንግሊዝና የፈረንሣይ መንግሥታትም፣ በየወሰናቸው ላይ ኢትዮጵያ በየጊዜው በምትጥልባቸው አደጋ እጅግ የተማረሩ በመሆናቸው፣ ዛሬ ጣልያን ደረሰብኝ ብላ ለምትጠይቀው ፍርድ፣ አብረዋት እንደሚሰለፉ ተስፋ ማድረግ ይቻላል። ስለዚህ፣

1ኛ/ ጠቡን ለመጫርና ውጊያውን ለማካሄድ የሚደረገው ዝግጅት በጥንቃቄ የተጠና እንዲሆን፣

2ኛ/ ኢትዮጵያ ያደረሰችብንን ጥቃት ለዓለም ሕዝብ ለማስረዳት የሚደረገው የፕሮፖጋንዳ ዘመቻና፣ ለሊግ ኦፍ ኔሽን የሚቀርበው መግለጫ፣ ከቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መንግሥት አቤቱታ እጅግ የቀደመ እንዲሆን፣

ያስፈልጋል ሲሉ፣ ኤክስፐርቶቹ ዝርዝር ጥናታቸውን ለክቡር ዱቼ አቀረቡ።

በመሠረቱ ሙሶሊኒ፣ የኢትዮጵያን ነፃነት ገፎ ቅኝ ግዛቱ ለማድረግ እጅግ የቸኮለ ቢሆንም፣ አስተማማኝ የሆነ የጦር ኃይልና የፕሮፖጋንዳ ዝግጅት ማስፈለጉን ደህና አድርጐ ስለሚያውቅ፣ የቀረበለት ፕላን ጊዜ የሚፈጅ ነው ብሎ አልተቆጣም። የጦርና የሲቪል ሹማምንቶቹም፣ ላቀረቡት ሐሳብ የዱቼን መልካም ፈቃድ ካገኙ በኋላ፣ ጠቡን ለመጫር አማካዩ ቦታ የት ቢሆን ይሻላል ? ብለው ሲያጠኑ፣ በደቡብ ምሥራቅ ኢትዮጵያ በኦጋዴን ግዛት ውስጥ በሚገኘው "ወልወል" በተባለው ቦታ ላይ እንዲሆን ተስማሙ። ሙሶሊኒ ራሱ እየተቆጣጠረ በተዘጋጀው ፕላን፣ ትልቁ የፋሽስት ጦር የሚሰፍረው፣ በሰሜን በኤርትራ በኩል ሲሆን፣ ግጭቱ የሚፈጠረው፣ በደቡብ በሱማሌ ወሰን ላይ እንዲሆን የተፈለገበት ምክንያት፣ በዚያ አካባቢ የተመደቡት የኢትዮጵያ የጠረፍ ሹማምንቶች፣ ዘመናዊ

የሆኑ የራዲዮ መገናኛዎች የሌሏቸውና ወታደሮቻቸውም የፋሽስትን ጦር የሚመክት ትጥቅና ስንቅ እንደሌላቸው ስለታወቀ ነበር።

"ወልወል" የተባለው ቦታ የሚገኘው፤ ከጣልያን ሱማሌ ወሰን አንድ መቶ ኪሎ ሜትር ያህል ርቆ በኢትዮጵያ የኦጋዴን ግዛት ውስጥ መሆኑ ታውቋል። ምንም እንኳ በኢትዮጵያና በጣልያን ሱማሌ መካከል ያለው ወሰን በሕግ ያልተከለለ ቢሆንም፤ እ.ኤ.አ በ1908 ዓ.ም ዳግማዊ ምኒልክና የጣልያን መንግሥት ባደረጉት ጠቅላላ ስምምነት፤ "ወልወል" በኢትዮጵያ ግዛት ውስጥ የሚገኝ መሆኑን፤ ራሳቸው ጣልያኖች ባወጡት ካርታ ላይ አመልክተውታል።

እ.ኤ.አ ከመስከረም 1934 ዓ.ም ጀምሮ ኢትዮጵያና እንግሊዝ በስምምነት አንድ የጋራ ኮሚሽን አቋቁመው፤ የሱማሌ ሕዝቦች ከብቶቻቸውን ለግጦሽ ሳር ወደ ኦጋዴን ግዛት እያሻገሩ ሲጠቀሙበት የቆየውን ልማድ፤ ወደፊት በተሻለና ችግር በሌለው መንገድ ለማስፈጸም ስለሚቻልበት ጉዳይ፤ ጥናት በማድረግ ላይ ይገኙ ነበር። እነዚህ የሁለቱ አገሮች የጋራ ኮሚሽን አባሎች፤ ከሰሜን የብሪቲሽ ሱማሌ ላንድ ጀምሮ ጥናታቸውን እያካሄዱ ወደ ደቡብ ኦጋዴን በመጓዝ ህዳር 23 ቀን 1934 ዓ.ም፤ **"ወልወል"** ላይ ሲደርሱ፤ **" ባንዳ "** የተባለው የጣልያን ሱማሌ የጦር ኃይል ሰፍሮበትና የመተላለፊያ መንገዱንም ዘግቶት አገኙት። ይህ ሁኔታ ከዚህ በፊት ያልነበረ አዲስ ነገር ስለሆነ፤ ከኢትዮጵያ በኩል የኮሚሽኑ መሪ የሆኑት ፊታውራሪ ተሰማ ባንቴና የኮሚሽኑ የፀጥታ ሹም ፊታውራሪ ሽፈራው፤ የባንዳው ጦር አዛዥ የሆነውን ካፒቴን ሲማሩታን (Cap. Simmaruta) የኢትዮጵያ ግዛት በሆነው ቦታ ላይ ምን ታደርጋላችሁ ? ብለው ሲጠይቁት የሰጣቸው መልስ፤ « ... **ወልወል ከብዙ ዓመታት ጀምሮ የጣልያን ሱማሌ ግዛት ስለሆነ፤ ይልቁንስ እናንተ በምን ምክንያት ወሰን ጥሳችሁ እዚህ መጣችሁ ? ...** » የሚል ሆነ። የካፒቴኑ አነጋገርና አኳኋን ለጠብ መዘጋጀቱን በግልጽ ስለሚያሳይ፤ ፊታውራሪ ሽፈራው በለሰለሰ ቃል፤ « ... **ወልወል የኢትዮጵያ ግዛት ሆኖ የኖረ ነው። በስሕተት የናንተ መስሏችሁ እንደሆነ፤ ያሰፈራችሁትን የጦር ኀዝ ይዛችሁ በእርጋታ ወደ ግዛታችሁ እንድትመለሱ ጊዜ እንሰጣችኋለን። አሁን የኢትዮጵያና የእንግሊዝ የጋራ ኮሚሽን አባሎች እዚህ የተገኙት፤ ስለ ግጦሹ ጉዳይ ጥናታቸውን ለማከናወን ስለሆነ፤ የዘጋችሁብንን መንገድ ክፈቱልን ....** » ብለው ጠየቁ። የካፒቴን ሲማሩታ (Simmaruta) መልስ **" አይቻልም"** ብቻ ሳይሆን ንቀትንና ዘለፋንም የያዘ ነበር። በዚህ ጊዜ የእንግሊዙ ኮሚሽን መሪ ኮሎኔል ክሊፎርድ (Col. Clifford) ባንዳዎቹ ለውጊያ ተዘጋጅተው መጠበቃቸውን ስለተረዳው፤ ችግሩን በሰላማዊ መንገድ ለመፍታት እንዲቻል በበኩሉ የተቻለውን ሙከራ ቢያደርግም፤ ካፒቴን ሲማሩታ ሊተባበረው አልፈለገም። ይልቁንም የባንዳው ጦር አባሎችና የኢትዮጵያ ፀጥታ አስከባሪዎች ፊት ለፊት ሆነው ጉዳያቸውን በሚነጋገሩበት ጊዜ፤ የመለያ ቁጥራቸው № S.O.4 እና S.O.7 የሆኑ፤ ሁለት የጣልያን የጦር አውሮፕላኖች ወደ መሬት ዝቅ ብለው እያንዣበቡና መትረየሳቸውን በኢትዮጵያውያኖቹ ላይ እየደገኑ ከፍተኛ የማስፈራሪያ ትርዒታቸውን ቀጠሉ። በዚህ ሁኔታ ጉዳዩ ምንም ዓይነት የሰላም መፍትሔ የሚገኝለት መስሎ ስላልታየው፤ **እንግሊዙ ኮሎኔል ክሊፎርድ፤ የጣልያን ባንዳ መሪ የወሰደው እርምጃ ሁሉ እጅግ የሚያሳዝንና የሚወገዝ መሆኑን በመግለጽ፤ ኮሚሽኑ ሥራውን አቋርጦ ለመመለስ መወሰኑን ለካፒቴን ሲማሩታ በጽሑፍ አስታወቀው።** የባንዳዎቹ መሪ ወዲያውኑ በሰጠው መልስ፤ ኢትዮጵያውያኖቹን በመከልከል፤ የእንግሊዝ ኮሚሽን አባሎች ሥራቸውን ለመቀጠል እንዲችሉ፤ የተዘጋው መተላለፊያ የሚከፈትላቸው መሆኑን ገለጸ። ኮሎኔል ክሊፎርድ ግን፤ የሁለቱ አገሮች የእንግሊዝና የኢትዮጵያ የጋራ ኮሚሽን

አባሎች የተሰጣቸውን ኃላፊነት የሚያከናውኑት በአንድነት ስለሆነ፣ ከካፒቴን ሲማሩታ የቀረበውን ሐሳብ የማይቀበል መሆኑን ካስታወቀ በኋላ ከወልወል ተነሥቶ ሠላሳ ኪሎ ሜትር ያህል ርቆ ወደሚገኘው አዶ (ADO) ወደተባለው ቦታ በመሔድ ድንኳኑን ተክሎ ሠፈረ።

ቀደም ሲል እንደተገለጸው፣ የሙሶሊኒ መንግሥት ኢትዮጵያን ለመያዝ ያቀደውን የወረራ ፕላን ለመጀመር አንድ መነሻ ምክንያት ስለሚያስፈልገው፣ ለእነዚህ ወሰን ጥሰው "ወልወል" በተባለው የኢትዮጵያ ግዛት ላይ እንዲሠፍሩ ለተደረጉት የጣልያን ባንዳ ወታደሮች የተሰጣቸው መምሪያ፣ ከአገሩ ፀጥታ አስከባሪዎች ጋር ግጭት ፈጥረው፣ ጦርነቱ እንዲከፈት ነው። በዚህም መሠረት፣ ለውጊያው የተሰናዱት የባንዳ ወታደሮች፣ በጀርባቸው ተዘጋጅቶ በሚጠብቃቸው የፋሽስት ፈጥኖ ደራሽ የአየር ኃይልና የምድር ጦር ሠራዊት ስለሚተማመኑ፣ እ.ኤ.አ ከህዳር 23 ቀን 1934 ዓ.ም ጀምሮ፣ ለዐሥር ቀናት ያህል ባለማቋረጥ የኢትዮጵያን ፀጥታ ጠባቂዎች ትዕግሥት ለማስጨረስና ጠቡን ለመጫር ያላደረጉት ሙከራ አልነበረም።

ኢትዮጵያውያኖቹ ግን፣ ቦታቸውን አጠንክረው ከመያዝና ከሰላም ፈላጊነት አቋማቸው የማይዛቡ በመሆናቸው፣ በዱቼ ልዩ ትዕዛዝ እ.ኤ.አ ታህሣሥ 5 ቀን 1934 ዓ.ም ከእኩለ ቀን በኋላ በዘጠኝ ሰዓት ተኩል ባንዶቹ ራሳቸው የመጀመሪያውን ጥይት በማጮህ ግጭቱ እንዲከፈት አደረጉ። አልሞት ባይ ተጋዳይ የሆኑትም ጥቂቶቹ የኢትዮጵያ ፀጥታ አስከባሪዎች፣ ባልተዘጋጁበትና ባልጠበቁት መንገድ የመጣባቸውን ጥቃት፣ እስከሚቻላቸው ድረስ መከላከላቸውን ቀጠሉ። እነዚህ ቁጥራቸው ወደ ስምንት መቶ የሚጠጋው ግንባር ቀደሞቹ የባንዳ ወታደሮቹም በታዘዙት መሠረት ውጊያውን እንደጀመሩ፣ ከጀርባቸው ተዘጋጅቶ የሚጠብቃቸው ጦር በታንክና በከባድ መሣሪያ ተደግፎ ሲደርስላቸው፣ ሦስት የአየር ኃይል አውሮፕላኖች ደግሞ ወደ መሬት ዝቅ ብለው በመብረር፣ በኢትዮጵያውያኖቹ ላይ የመትረየስ ተኩስና የቦንብ አሎዳ አዘነቡባቸው።

በዚህ በሮብ ቀን እ.ኤ.አ ታህሣሥ 5/1934 ዓ.ም ከሰዓት በኋላ ከዘጠኝ ተኩል እስከ ምሽቱ አንድ ሰዓት ድረስ፣ የፋሽስት ጦር የኢትዮጵያ ግዛት በሆነው "ወልወል" ላይ በጣለው አደጋ አንድ መቶ ሰባት (107) ኢትዮጵያውያኖች ሲሞቱ፣ በጽኑ የቆሰሉት ደግሞ አርባ አምስት (45) ሆኑ። ከሞቱትም መካከል የታወቁት የጦር አለቃ ፊታውራሪ ዓለማየሁ ጉሹ ይገኙበታል። የኢትዮጵያ ፀጥታ አስከባሪዎች፣ ቀደም ሲል ተዘጋጅቶ ከመጣባቸው ጠላት፣ ከሰማይ የአውሮፕላን ቦንብ እየወረደባቸው፣ በምድር በታንክና በከባድ መሣሪያዎች የሚተኮስባቸውን እየተጋፈጡ፣ ያሏቸውን ቀላል የሆኑ መትረየሶችና ጠብመንጃዎች ብቻ በመጠቀም፣ በገጠሙት ውጊያ፣ ከፋሽስት የጦር ወታደሮች መካከል ዘጠናዎቹ (90) መገደላቸው ታውቋል።

ከዚህ በላይ እንደተገለጸው፣ የፋሽስት ወታደሮች ወልወል ላይ ያደረሱትን አደጋ ዝርዝር ታሪኩን በመተንተን፣ የኢትዮጵያ ኮሚሽን ባለሥልጣኖች በዚያኑ ዕለት ምሽት ለንጉሠ ነገሥቱ መንግሥት የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር በቴሌግራም ሲያመለክቱ፣ ብላቴን ጌታ ኅሩይ ወልደሥላሴም ወዲያውኑ የሚከተለውን እርምጃ ወሰዱ።

አዲስ አበባ ያለውን የጣልያንን ለጋሲዮን ጉዳይ ፈጻሚ ሲኞር ሞምቤሊን በጽሕፈት ቤታቸው አስጠርተው፤

1ኛ/ በሱማሌ ያለው የጣልያን አስተዳደር መንግሥት፤ የኢትዮጵያን ወሰን ጥሶ አንድ መቶ ኪሎ ሜትር ያህል ወደ ውስጥ ዘልቆ በሚገኘው "ወልወል" በተባለው ግዛታችን ላይ የጦር ኃይል አስፍሮ መገኘቱን፤

2ኛ/ የኢትዮጵያና የእንግሊዝ የጋራ ኮሚሽን አባሎች ስለ ግጦሽ ጉዳይ የሚያደርጉትን ጥናት ለማከናወን ሲዘዋወሩ፤ ይህ "ወልወል" ላይ ሰፍሮ የጠበቃቸው የጣልያን መንግሥት የጦር ኃይል መንገዱን ዘግቶ እንደከለከላቸው፤

3ኛ/ የኢትዮጵያና የእንግሊዝ የጋራ ኮሚሽን መሪዎች፤ ፊታውራሪ ተሰማ በንቲና ኮሎኔል ክሊፎርድ (Col. Clifford) ከሕግ ውጭ ወልወል ላይ የተፈጠረባቸውን ችግር በሰላም መንገድ ለመፍታት ያደረጉትን ጥረት ሁሉ፤ የጣልያን ሱማሌ ጦር አዛዥ ካፒቴን ሲማሩታ (CAP.SIMMARUTA) በንቀት መንፈስና በዘለፋ አነጋገር አልቀበልም በማለቱ፤ የኮሚሽኑ ሥራ እንዲቋረጥ መደረጉን፤

4ኛ/ የጋራው ኮሚሽን አባሎች ሥራቸውን እንዲያቋርጡ ተገድደው፤ ከወልወል ሠላሳ ኪሎ ሜትር ርቆ ከሚገኘው "አዶ" (ADO) ከተባለው ቦታ ከሠፈሩ በኋላ፤ ወደፊት ምን ማድረግ እንደሚኖርባቸው ከየመንግሥታቸው መምሪያ በሚጠባበቁበት ጊዜ፤ የጣልያን ሱማሌ ጦር አዛዥ ግጭት ለመፍጠር ላደረጋቸው ሙከራዎች ሁሉ የኢትዮጵያ ፀጥታ አስከባሪዎች፤ ሰላም ፈላጊነታቸውን ከማስገንዘብ በስተቀር፤ እንዳች የጠብ መንፈስ ሳያሳዩ በትዕግሥት መቆየታቸውን፤

5ኛ/ ካፒቴን ሲማሩታ፤ ለዐሥር ቀናት ያለማቋረጥ ከኢትዮጵያ ፀጥታ አስከባሪዎች በኩል ጠብ እንዲተነኮስ የሞከረው ሁሉ የማይሳካለት መሆኑን ሲገነዘብ፤ ታህሣሥ 5 ቀን 1934 ዓ.ም ከሰዓት በኋላ በዘጠኝ ሰዓት ተኩል፤ እሱ ራሱ ተኩሱን ከፍቶ በተደረገው ውጊያ፤ አንድ መቶ ሰባት (107) ኢትዮጵያውያኖች መገደላቸውንና አርባ አምስት (45) መቁሰላቸውን፤

6ኛ/ የጣልያን መንግሥት ጦር ወሰን ጥሶ፤ በኢትዮጵያውያኖች ላይ ይህንን የሚያህል አደጋ ለማድረስ የቻለው፤ ወልወል ላይ ባሰለፋቸው በብዙ መቶ በሚቆጠሩት የባንዳ ወታደሮቹ ብቻ ሳይሆን፤ ከጀርባው በተዘጋጁለት የቦንብ ጣይ አውሮፕላኖችና በታንክ በተጠመዱ መድፎች መሆኑን፤ የንጉሠ ነገሥቱ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር፤ ክቡር ብላቴን ጌታ ኅሩይ ወልደሥላሴ፤ ለጣልያን ለጋሲዮን ጉዳይ ፈጻሚ ለሲኞር ሞምቤሊ (Mombelli) መጀመሪያ በቃል፤ ወዲያውኑም አከታትለው በጽሑፍ፤ ከፍተኛ ተቃውሞአቸውን ካስታወቁ በኋላ፤ የሙሶሊኒ መንግሥት በአስቸኳይ መልሱን እንዲሰጣቸው ጠየቁ።

# የማን አስብኝ መልስ

ከዚህ በላይ እንደተገለጸው፣ የኢትዮጵያ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር አዲስ አበባ ለሚገኘው የጣልያን ሌጋሲዮን ላቀረቡት ተቃውሞ ከሁለት ቀናት በኋላ፣ የፋሽስቱ መንግሥት በማን አስብኝና በአምባገነንነት መንፈስ የሚከተለውን መልስ ሰጣቸው።

ሀ/ "ወልወል" ከብዙ ዓመታት ጀምሮ የጣልያን ግዛት ሆኖ የኖረ ነው።

ለ/ ታህሣሥ 5 ቀን 1934 ዓ.ም የኢትዮጵያ ወታደሮች የወልወልን ወሰን ጥሰው ተኩስ በመክፈት ባደረሱት ከፍተኛ አደጋ፣ ቁጥራቸው ለጊዜው ሊታወቅ ያልቻለ የብዙዎች ዜጎቻችን ሕይወት አልፏል።

ይህ የኢትዮጵያ መንግሥት የፈጸመብን የግፍ ሥራ፣ በአገሮቻችን መካከል ያለውን ግንኙነት ወደ ከፋ ሳያመራ በሰላማዊ መንገድ እንዲያልቅ ከተፈለገ፣ የጣልያን መንግሥት የሚከተሉትን ዋና ዋና ጉዳዮች በአስቸኳይ እንዲፈጸሙለት በጥብቅ ይጠይቃል። እነዚህም፣

1ኛ/ የሐረሩ ገዥ ደጃዝማች ገብረማርያም ጋሪ፣ "ወልወል" ድረስ መጥተው በዚያ ለሚገኘው የጦር ሠፈራችን የይቅርታ ልመና በማቅረብ፣ ለገናናው የጣልያን መንግሥት ባንዲራ የክብር ሰላምታ እንዲሰጡ፣

2ኛ/ ግጭቱን ፈጥረው አደጋውን ያደረሱት የኢትዮጵያ የጦር ኃላፊዎች ተይዘው ተገቢው ቅጣት እንዲፈጸምባቸው፣

3ኛ/ በጣልያን ሱማሌ ግዛት ውስጥ ወንጀል ከፈጸመ በኋላ ሸሽቶ ወደ ኢትዮጵያ የገባው አማር ሳማንታር የተባለው ዜጋችን፣ እጁ ተይዞ ወልወል ለሚገኙት ኃላፊዎቻችን እንዲሰጥ፣

4ኛ/ በጣልያን ሱማሌ ዜጎቻችን ላይ ለተፈጸመባቸው ግፍ፣ የኢትዮጵያ መንግሥት ሁለት መቶ ሺህ የማሪያ ቴሬዛ ብር (200.000) ካሣ እንዲከፍል ያስፈልጋል ሲል፣ ዕብሪተኛው የሙሶሊኒ መንግሥት በይፋ ጠየቀ።

የጥንታዊት የጀግኖች አገር ኢትዮጵያ፣ የቴዎድሮስ ኢትዮጵያ፣ የዮሐንስና የምኒልክ ኢትዮጵያ፣ ይህንን የመሰለ የውርደት ግዴታ ትቀበላለች ብሎ ማሰብ ስለማይቻል፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ጉዳዩ በመንግሥታት ማህበር ዳኝነት እንዲታይላቸው ወሰኑ። ኀሩይ ወልደሥላሴ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር፣ እ.ኤ.አ ታህሣሥ 14 ቀን 1934 ዓ.ም ለመንግሥታት ማህበር በላኩት ቴሌግራም፣ የፋሽስት መንግሥት በኦጋዴን በኩል ያለውን ወሰን ጥሶ፣ አንድ መቶ ኪሎ ሜትር ወደ ውስጥ ዘልቆ የሚገኘውን ወልወል የተባለውን የኢትዮጵያን ግዛት በጦር ኃይል

ይዞ፤ በኢትዮጵያውያኖች ላይ ያደረሰውን ከፍተኛ ጉዳት ዘርዝረው ገለጹ። *

ኢትዮጵያ ሰላም ፈላጊ ስለሆነች፤ ከጣልያን መንግሥት ጋር እ.ኤ.አ በ1928 ዓ.ም በፈረመችው ውል መሠረት፤ በወልወል ላይ የደረሰው ግጭት፤ ጥፋቱ ከማን በኩል እንደሆነ በጋራ በሚመረጡ ሽማግሌዎች እንዲመረመር ያቀረበችውን ሐሳብ የሮማ መንግሥት አልቀበልም የሚል መልስ ስለሰጠ፤ ጉዳዩ እጅግ አሳሳቢ ሆኗል። ስለዚህ፤ የመንግሥታት ማህበር በአባል አገሮች መካከል ለሚፈጠረው አለመግባባት መፍትሔ ለመስጠት ያለበትን ኃላፊነት እንዲፈጽም ኢትዮጵያ ትጠይቃለች ሲሉ አመለከቱ። ይህ የኢትዮጵያ አቤቱታ ዤኔቭ ሲደርስ፤ የሙሶሊኒ መንግሥት ምንም ዓይነት ድምጽ አላሰማም ነበር።

ስለ ሙሶሊኒ የጦርና የፕሮፖጋንዳ ዝግጅት፤ ከዚህ በፊት በተነበበው ምዕራፍ ፩ ላይ እንደተገለጸው፤ የፋሽስት ሊቃውንቶች አጥንተው ባዘጋጁት ፕሮግራም፤ ለወረራው መነሻ ምክንያት የሚሆነው የጠረፍ ግጭት እንደተደረገ፤

1ኛ/ ኢትዮጵያ ወሰን ጥሳ በጣልያን ዜጐች ላይ ከፍተኛ ጉዳት አድርሳለች በማለት የፋሽስት መንግሥት ከአዲስ አበባ ቀድሞ ለዤኔቭ የመንግሥታት ማህበር ክስ እንዲያቀርብ፤

2ኛ/ የዓለምን ሕዝብ አስተያየት ለመማረክ እንዲቻል፤ በጋዜጦችና በዜና ማሰራጫ ድርጅቶች አማካይነት፤ ኢትዮጵያ የፈጸመችውን በደል በዝርዝር እንዲያሰራጭ፤ ተወስኖ እንደነበረ ይታወሳል።

ነገር ግን፤ እጅግ አስገራሚ ሆኖ የሚታየው፤ የወልወል ግጭት በደረሰ በዘጠነኛው ቀን የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መንግሥት ለሊግ ኦፍ ኔሽን አቤቱታውን በማቅረብ ከሙሶሊኒ ቀድሞ መገኘቱ ነው። ለመንግሥታት ማህበር ለማመልከት ቀደም ብሎ አስቦበት የነበረው የሙሶሊኒ መንግሥት፤ ከኢትዮጵያ የዘገየው ለምን እንደሆነ ምርምር ሲደረግ፤ የፋሽስቶች ጉዳይ አዋቂ የሆነው ፕሮፌሰር ሬንሶ ደ-ፌሊቼ (RENZO DE-FELICE) ሁለት ዓይነት ምክንያቶች ሰጥቷል። የመጀመሪያው፤ በፋሽስትነቷ ተራምዳ በዓለም ላይ ከፍተኛ ደረጃ ያገኘችው ጣልያን፤ እንዴት አድርጋ አንዲት እጅግ ወደ ኋላ የቀረች ድሃ አገር አጠቃችኝ ብላ፤ ከመንግሥታት ማህበር ፍርድ ትጠይቃለች ? በሚል የንቀት መንፈስ ክቡር ኮማንዳቶሬ ዱቼ ከልክሎ ይሆናል የሚባለው ነው። ሁለተኛው ምክንያት ደግሞ፤ ጎሩይ ወልደሥላሴ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር፤ የወልወል ግጭት ከደረሰበት ዕለት ጀምሮ፤ ከጣልያን መንግሥት ጋር ሰፊ የሆነ የዲፕሎማቲክ ድርድር በማድረግ ላይ ስለነበሩ፤ በድንገት አቋርጠው ወደ ዤኔቭ ክስ ለማቅረብ ይፈጥናሉ ብለው የዱቼ የውጭ ጉዳይ ባለሥልጣኖች ባለመገመታቸው ሊሆን ይችላል የሚለው አስተያየት ነው።

ያም ሆነ ይህ፤ ኢትዮጵያ በጉልበተኛው ፋሽስት በወልወል ግዛቷ ላይ የደረሰባትን ጥቃት፤ ለመንግሥታት ማህበር ከጠላቷ ቀድማ ያመለከተችው፤ የተለየ የፍርድ አስተያየት ሆነ የፕሮፖጋንዳ ጥቅም አገኝበታለሁ ብላ በማሰብ

* ከዚህ ቀደም ለጣልያን መንግሥት ዝርዝሩን በጽሑፍ እንዳስረዱት ዓይነት

# ደጃዝማች አፈወርቅ ወልደ ሰማያት






ሶማሌ ክልል

ደጃዝማች አፈወርቅ ወልደሰማያት

በደቡብ ኢትዮጵያ በሱማሌ በኩል ፋሽስት አገራችንን ለመውረር በሚዘጋጅበት ጊዜ፣ ግራዝማች አፈወርቅ ወልደሰማያት በኦጋዴን ግዛት "ቆራሄ" ላይ ለሰፈሩት የኢትዮጵያ ፀጥታ አስከባሪ ወታደሮች አዛዥ ነበሩ። ከወልወል ግጭት በኋላ ጠላት የአየርና የምድር ኃይሉን አዘጋጅቶ አገራችንን መውረር ሲጀምር፣ ግራዝማች አፈወርቅ እስከ ሕይወቱ ፍጻሜ ድረስ የአገሬን መሬት አላስነካም፣ ለጠላትም እጄን አልሰጥም ብለው፣ በነበራቸው ጥቂት መሣሪያ ያለማቋረጥ ሲዋጉ በጠላት ጥይት ተመትተው ሕይወታቸው አለፈ። ንጉሠ ነገሥቱም ከአዲስ አበባ እስከ ኦጋዴን በአውሮፕላን ሄደው፣ በጀግናው መቃብር ላይ "አፈወርቅ ደጃዝማች" የሚል የመታሰቢያ ስም ሰጥተው ተመለሱ። አፈወርቅ ይህንን ታሪካዊ ጀግንነት የፈጸሙት በሰላሣኛው ዕድሜያቸው ነበር።

አልነበረም። ነገር ግን፤ ፋሽስቶቹ ሊቃውንቶች ቀደም ሲል እንደመከሩት፤ « ... ኢትዮጵያ ድንበር ጥሳ በዜጎቼ ላይ ከፍተኛ አደጋ አደረሰችብኝ ... » በማለት፤ ዱቼ ሙሶሊኒ በገኔቭ መድረክ ላይ ጩኸቱን ቢያሰማ ኖሮ፤ ያለጥርጥር አብረውት የሚያሜፍሩት የመንግሥታት ማህበር አባሎች እንደሚያገኝና፤ በአንዳንድ አገሮችም ዘንድ ይህች ኢትዮጵያ ለምን አርፋ አትቀመጥም? የሚል አስተያየት ለመቃረም የሚያስችለው ይሆን ነበር።

ይሁን እንጂ፤ ሙሶሊኒ ክሱን ከኢትዮጵያ በኋላ ዘግይቶ ቢያቀርብም፤ ምንም ዓይነት ጉዳት አልደረሰበትም። የሊግ ኦፍ ኔሽን ዋና ጸሐፊ ዮሴፍ አቬኖል (JOSEPH AVENOL) የዱቼ አድናቂና የፋሽስቶች ዋና ወዳጅ በመሆኑ፤ ኢትዮጵያ በአስቸኳይ ቴሌግራም ያቀረበችውን አቤቱታ፤ ለየመንግሥታቱ እንደራሴዎች ወዲያውኑ በማሰራጨት ፋንታ፤ ከጣልያን መንግሥት የሚቀርበው ክስ እስኪደርሰው ድረስ አንቆ በመያዝ፤ ከፍተኛ እርዳታ አድርጉለታል። በዚያን ጊዜ በገኔቭ የኢትዮጵያ ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትርና ልዩ መልዕክተኛ የነበሩት ፊታውራሪ ተክለሐዋርያት፤ ዋናው ጸሐፊ በሚሠራው ተንኮል በመበሳጨት በቀጠሮ እቢሮው ድረስ ሄደው፤ « ... አንተ፤ በእምነትህም ሆነ በሥራህ ፋሽስት መሆንህን ስለአስመሰከርክ፤ የመንግሥታት ማህበር ዋና ጸሐፊ ነኝ ከማለት ይልቅ፤ የሙሶሊኒ እንደራሴ መሆንህን በይፋ ብታስታውቅ ይሻልሀል ... » በማለት አወገዙት። አቬኖልም በበኩሉ ከፍተኛ ቅሬታ ገብቶት፤ « ... የኢትዮጵያ ሚኒስትር ስለሰደበኝ፤ ጉዳዩ በሊግ ኦፍ ኔሽን ካውንስል እንዲታይልኝ ... » ብሎ በተነሣ ጊዜ፤ ተክለሐዋርያት ለማንም የማይመለስ አደገኛ ስለሆነ፤ ምን ዓይነት ወንጀል እንደሚጥልብህ አይታወቅምና መታገሥ ይሻልሀል ብሎ የመከረው፤ የፋሽስት መንግሥት እንደራሴ ባሮን አሉይዚ (BARON ALOISI) ነበር።

ፊታውራሪ ተክለሐዋርያት እንደተናገሩት፤ ዮሴፍ አቬኖል (JOSEPH AVENOL) ከመንግሥታት ማህበር ዋና ጸሐፊነቱ ይልቅ፤ የፋሽስት አገልጋይነቱ ስለሚመዝን፤ ከኢትዮጵያ የቀረበውን አቤቱታ ለጣልያን የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር በቅድሚያ በመስጠት፤ የሙሶሊኒ መንግሥት በኢትዮጵያ ላይ ከዚህ የሚከተለውን ክስ አዘጋጅቶ እንዲያቀርብ አስደረገ።

1. "ወልወል" የተባለው ቦታ ጥንቱንም የጣልያን ሱማሌ ግዛት ሆኖ የኖረና ከብዙ ዓመታት ጀምሮ ቁጥራቸው ሁለት መቶ የሚደርስ የጣልያን ፀጥታ አስከባሪዎች ሰፍረውበት የቆየ ነው።

2. እ.ኤ.አ ህዳር 23 ቀን 1934 ዓ.ም፤ ስለ ግጦሽ ጉዳይ እናጠናለን የሚሉ የኢትዮጵያና የእንግሊዝ የጋራ ኮሚሽን አባሎች፤ ቁጥራቸው አንድ ሺህ (1000) በሚሆኑ የኢትዮጵያ ወታደሮች ታጅበው "ወልወል" ሲደርሱ፤ የጣልያን የፀጥታ ሹም በዚህ በኩል ማለፍ እንደማይችሉ አስታወቃቸው።

3. የኢትዮጵያ ኮሚሽን ኃላፊ "ወልወል" የኛ ግዛት ስለሆነ ልትከለክሉን አትችሉም ሲል ክርክር ባነሣ ጊዜ፤ ስለ ግዛቱ ባለቤትነት ጉዳይ መነጋገር የሚያስፈልገው በሁለቱ አገሮቻችን መንግሥታት መካከል ነው እንጂ፤ በእኛ ደረጃ አይደለም በማለት ካፒቴን ሲማሩታ ተገቢውን መልስ ሰጠ።

4. የሁለቱ አገሮች የጋራ ኮሚሽን አባሎች ሁኔታውን ተረድተው ወደ ኋላ በመመለስ "አዶ" (ADO) ላይ ሔደው ሲሰፍሩ፤ ቁጥራቸው ከአንድ ሺህ በላይ የሆኑት የኢትዮጵያ የጦር ሠራዊት፤ የጣልያን ወታደሮች ካሉበት ፊት ለፊት ቦታ ይዘው፤ ለዐሥር ቀናት ያህል ባለማቋረጥ ጠብ ለመጫር ሲሞክሩ ሰነበቱ።

5. ታህሣሥ 5 ቀን 1934 ዓ.ም ከእኩለ ቀን በኋላ፤ ጠብ ለማንሣት ሲዘጋጁ የሰነበቱት የኢትዮጵያ ወታደሮች፤ ያለ አንዳች ምክንያት በጣልያን ሱማሌዎች ላይ ተኩስ ከፍተው ማጥቃት ጀመሩ። ጣልያኖቹም በበኩላቸው በሚቻላቸው ሁሉ መከላከላቸውን ሳያቋርጡ፤ ረዳት ጦር እንዲደርስላቸው በራዲዮ ለመንግሥት ባመለከቱት መሠረት፤ ጥቂቶች የቦንብ ጣይ አውሮፕላኖችና ታንክ ተልኮላቸው፤ አጥቂዎቹን የኢትዮጵያን ወታደሮች ለማባረር ቻሉ። በዚህ ባልታሰበና ባልተጠበቀ ውጊያ ለጊዜው ቁጥራቸው ምን ያህል እንደሆነ ባይታወቅም፤ የብዙዎች ዜጎቻችን ሕይወት ማለፉ ታውቋል።

6. የኢትዮጵያ መንግሥት ግዛታችን ድረስ ጦር ልኮ በዜጎቻችን ላይ ይህን አደጋ ባደረሰ ጊዜ፤ የጣልያን መንግሥት ወዲያውኑ አዲስ አበባ ባለው ለጋሲዮኑ በኩል ብርቱ ተቃውሞውን ካቀረበ በኋላ፤ በሁለቱ አገሮቻችን መካከል ሰላም እንዲኖር ከተፈለገ፤

   ሀ/ የሐረሩ ጠቅላይ ገዥ፤ ወልወል ግዛታችን ድረስ መጥቶ፤ ለሰንደቅ ዓላማችን ሰላምታ በመስጠት ይቅርታ እንዲጠይቅ፣

   ለ/ በጣልያን የፀጥታ ጠባቂዎቻችን ላይ ተኩስ ከፍተው ይህንን ከባድ አደጋ ያደረሱብን የኢትዮጵያ የጦር ኃላፊዎች ለፍርድ ቀርበው እንዲቀጡ፣

   ሐ/ በግፍ ለተገደሉትና ለቆሰሉት ዜጎቻችን የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መንግሥት ሁለት መቶ ሺህ የማሪያ ቴሬዛ ብር ካሣ እንዲከፍል፣

አግባቡ በሆነው በዲፕሎማቲክ ጉዳና በጽሁፍ ጠይቀን ነበር። ነገር ግን የኢትዮጵያ መንግሥት በሁለቱ አገሮቻችን መካከል በ1928 ዓ.ም የተፈረመውን ውል በመመርኮዝ፤ ሽማግሌዎች ተመርጠው ፍርድ ይስጡበት ሲል የሰጠውን መልስ፤ የጣልያን መንግሥት ሊቀበለው አይችልም። በወልወል ላይ ለደረሰው ግጭት፤ ኃላፊውና ተጠያቂው የኢትዮጵያ መንግሥት መሆኑ የተረጋገጠ ስለሆነ፤ የሽማግሌዎችን አስፈላጊነት የጣልያን መንግሥት አያምንበትም። ስለዚህ፤ በሁለቱ አገሮች መካከል የተፈጠረው ጠብ ወደ ሰላም ሊመለስ የሚችለው፤ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መንግሥት ከጣልያን መንግሥት ተዘርዝሮ የቀረበለትን ሲፈጽምና፤ በግፍ ለተገደሉትም ዜጎቻችን የተተመነውን ካሣ ሲከፍል ነው ሲል፤ የፋሽስት መንግሥት በአንድ በኩል ክሱን፤ በሌላ በኩል የራሱን ፍርድ ወስኖ የመንግሥታት ማህበር እንዲያስፈጽምለት ታህሣሥ 17 ቀን 1934 ዓ.ም አቀረበ።

እንግዲህ ! የዚህ የወልወል ግጭት ከተጀመረ አንሥቶ እስከዛሬ ያለውን ሂደት ስንመለከት፣ በዚያ ተለዋዋጭ በሆነው በአስቸጋሪው ዓለም ውስጥ፣ የአምባገነን መሪዎች አስተያየትና ፍርድ ምን ያህል አሳዛኝ እንደነበረ ለመገመት ያስችለናል። ከመንገድ ወሮበላነት ተነሥቶ በጣልያን ሕዝብ ላይ የነገሠው፣ ሙሶሊኒ የተባለው ዲክታተር፣ ራሱ ቀማኛ ራሱ ዳኛ መሆን እንደሚችል ስለአመነበት፣ ወደ ኢትዮጵያ ግዛት ጥሶ ገብቶ፣ የኢትዮጵያን መሬት ይዞ፣ አንድ መቶ ሰባት ኢትዮጵያውያኖችን ካስገደለ በኋላ፣ ኢትዮጵያ ስለደረሰባት ጉዳት፣

1ኛ/ ለፋሽስቱ ባንዲራ ዝቅ ብላ በታላቅ ትሕትና ሰላምታ በመስጠት ይቅርታ እንድትጠይቅ፣

2ኛ/ ሁለት መቶ ሺህ የማሪያ ቴሬዛ ብር ለፋሽስት መንግሥት ካሣ እንድትከፍል፣ ዲክታተሩ ዱቼ፣ የራሱን ፍርድ ሰጥቶ የመንግሥታት ማህበር እንዲያስፈጽምላት ሲጠይቅ፣ ምንም ዓይነት የይሉኝታ ስሜት ወይም የሕሊና ወቀሳ እንዳላደረበት ለማንም ግልጽ ነው። በጄኔቭ የሚገኙት የመንግሥታት እንደራሴዎችም፣ ኢትዮጵያ ያቀረበችላቸውን አቤቱታና ሲኞር ሙሶሊኒ እንዲፈጽሙ የጠየቃቸውን አጥንተው፣ ትክክለኛውን ፍርድ ለመስጠት አስበው ቢሆን ኖሮ፣ ወልወል ላይ ማን አጥቂ እንደሆነና ማን ተጠቂ እንደሆነ ለመለየት የሚያስቸግራቸው አልነበረም።

መጀመሪያ፣ "ወልወል" የተባለው ቦታ ከብዙ ዓመታት ጀምሮ በጣልያን ሱማሌ ግዛት ውስጥ የሚገኝ ነው ብሎ ያቀረበውን ክስ የፋሽስቱ መንግሥት የሚያምንበት ከሆነ፣ የቀረው ቢቀር የቅኝ አገሮቹ አስተዳደር ሚኒስቴር በ1934 ዓ.ም ነድፎ ባተመው ካርታ ላይ በምን ምክንያት ? ለማንስ ሲል ? "ወልወል" በኢትዮጵያ የኦጋዴን አውራጃ ውስጥ መገኘቱን አረጋገጠ ? ለዚህ ጥያቄ፣

የፋሽስቱ መንግሥት ትክክለኛውን መልስ መስጠት ካልቻለ፣ (ደግሞም አይችልም) ወልወል የኔ ግዛት ነው ብሎ ያቀረበው ክስ፣ በሚያሳፍር ውሸት ላይ የተመሠረተ ለመሆኑ ከዚህ የበለጠ ማስረጃ አያስፈልገውም።

ሁለተኛ/ ወልወል ላይ ግጭቱ እንዴት እንደተጀመረ፣ ሙሶሊኒ ባቀረበው ክስ ላይ እንዳስረዳው፣ « ... ታህሣሥ 5 ቀን 1934 ዓ.ም ከእኩለ ቀን በኋላ አንድ ሺህ የሚሆኑ የኢትዮጵያ ጦር ሠራዊት አባላት ቁጥራቸው ከሁለት መቶ በማይበልጡ የጣልያን ወታደሮች ላይ በድንገት ተኩስ ከፍተው አደጋ ሲጥሉባቸው፣ ቦንብ ጣይ አውሮፕላኖችና ታንክ ደርሰው፣ አጥቂዎቹን ኢትዮጵያውያኖች ለማባረር ችለዋል ... » ይላል። እንግዲህ ! በዚህ በታህሣሥ 5 ቀን 1934 ዓ.ም የኢትዮጵያ ወታደሮች ውጊያውን የከፈቱት ባልተጠበቀና ባልታሰበ ሰዓት ከሆነ፣ እነዚያ ቦንብ ጣይ አውሮፕላኖችና በታንክና በከባድ መሣሪያ የተደገፈ ጦር፣ አስቀድሞ ለማጥቃት ተዘጋጅተው በተጠንቀቅ ሲጠብቁ የነበሩ ካልሆኑ በስተቀር፣ በጥቂት ደቂቃዎች ውስጥ ከየት ተነሥተው፣ በምንስ ተአምር፣ ወልወል ላይ ጠብ ጫሪዎቹን ለመደምሰስ ቻሉ ? ... ለዚህ ጥያቄ የፋሽስቱ መንግሥት ምንም ዓይነት አጥጋቢ መልስ ስለሌለው፣ ይህ ጉዳይ ሁለተኛው ውሸት ሆኖ እንደሚቆጠር በትክክል መገንዘብ ይቻላል።

ሦስተኛ/ ስለ ግጦሹ ጉዳይ ጥናት እንዲያደርግ የተቋቋመው የእንግሊዝና የኢትዮጵያ የጋራ ኮሚሽን፣ እ.ኤ.አ ህዳር 23 ቀን 1934 ዓ.ም የኢትዮጵያ ግዛት በሆነው "ወልወል" ላይ ሰፍሮ መንገድ የዘጋበት የጣልያን ሱማሌ ጦር፣ ምን ያህል ችግር እንደፈጠረበትና በመጨረሻም ሥራውን አቋርጦ ወደ ኋላ ለመመለስ እንደተገደደ፣ የእንግሊዙ ኮሚሽን ኮሎኔል ክሊፎርድ (COL. CLIFFORD) ለበላዩ ባቀረበው ራፖር በዝርዝር አስረድቷል። በካፒቴን ሲማሩታ (CAP. CIMMARUTA) የሚታዘዘው የጣልያን ጦር፣ ኢትዮጵያውያኖቹን አለአግባብ እያበሳጨ ግጭት ለመፍጠር ያደረጋቸውን ሙከራዎችና፣ በዚያኑ ጊዜም የጣልያን የጦር አውሮፕላኖች ወደ መሬት ዝቅ እያሉ በማንዣበብ በጋራ ኮሚሽን አባሎች ላይ ያሳዩት የነበረውን ማስፈራራት በመግለጽ፣ ኮሎኔል ክሊፎርድ ምስክርነቱን ስለሰጠ፣ ለወልወል ግጭት ተጠያቂው የፋሽስት መንግሥት መሆኑን ለማመን፣ መረጃነቱ ሊያጠራጥር አይችልም።

አራተኛ/ ታህሣሥ 5 ቀን 1934 ዓ.ም ከእኩለ ቀን በኋላ ከዘጠኝ ሰዓት ተኩል እስከ ምሽቱ አንድ ሰዓት ተኩል ድረስ፣ ወልወል ላይ በደረሰው ግጭት፣ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መንግሥት ከኢትዮጵያ በኩል አንድ መቶ ሰባት (107) ሰዎች መገደላቸውንና አርባ አምስት ሰዎች መቁሰላቸውን በይፋ ሲያስታውቅ፣ ተጠቃሁ ! በዜጎቼ ላይ ከፍተኛ አደጋ ደረሰብኝ እያለ የሚጮኸው የፋሽስት መንግሥት፣ ምን ያህል ወታደሮች እንደሞቱበትና ምን ያህል ደግሞ እንደቆሰሉ መናገር አልቻለም። ስለዚህ፣ የኢትዮጵያ ጦር ሠራዊት ለገደላቸው ዜጎቼ ሁለት መቶ ሺህ (200.000) የማሪያ ቴሬዛ ብር ካሣ ሊከፈለኝ ይገባል ብሎ ያቀረበው የፋሽስት መንግሥት ሒሣቡን በምን እንደተመነው ማስረዳት አልቻለም።

በገኔቭ የመንግሥታት ማህበር ሸንጎ ላይ የሚካሄደው ፍርድ ሁሉ፣ ለትልቅ ወይም ለትንሽ ሳይል ለሁሉም እኩል ነው እየተባለ ሲነገር የኖረ መሆኑ ይታወሳል። ስለዚህም፣ በኢትዮጵያና በጣልያን መካከል ወልወል ላይ ስለደረሰው ግጭት፣ በመንግሥታት ማህበር የተሠየሙት ዳኞች ባደረጉት ምርምር፣ እውነት ተፈልፍላ ወጣች ? ወይስ ተቀብራ ቀረች ? ተብሎ ለሚቀርበው ጥያቄ፣ መልሱን በደረቁ በቀጥታ ዛሬውኑ ከመስጠት ይልቅ፣ ወደፊት የታሪኩን ሂደት እየተከተልን ስንጓዝ ብናገኘው ይሻላል።

1. Documents (Affaires Wolwol)
   c. 558.M. 258. 1934 VII.

2. J.O.L.S.D.N XVI — PP. 248 -49 (Journal De Societé Des Nations No 1615
3. FO371/18027

# ምዕራፍ ፫

## በኢትዮጵያ ላይ
## የላቫልና የሙሶሊኒ ስምምነት

« ... በኢትዮጵያ ጉዳይ ፈረንሣዮች በይፋ ባይደግፉኝም፣ ተቀዋሚዎቹ ሆነው እንደማያስቸግሩኝ ሙሉ ተስፋ አደርጋለሁ .... » (ሙሶሊኒ 25/12/1934)

እ.ኤ.አ በጥቅምት 30 ቀን 1922 ዓ.ም ሙሶሊኒ ጠቅላይ ሚኒስትር ሆኖ ሙሉ ሥልጣን ከያዘበት ጊዜ ጀምሮ፣ በጣልያንና በፈረንሣይ መካከል የነበረው ግንኙነት፣ ከዐሥር ዓመታት በላይ እጅግ ቀዝቅዞ እንደኖረ ይታወሳል። የፈረንሣይ ቅሬታ፣ እንዴት በሠለጠነው በአውሮፓው ዓለም ውስጥ፣ የዴሞክራሲ አስተዳደር ተወግዶ፣ በዲክታተር አመራር ይተካል ? በሚል አስተያየት ሲሆን፣ ሙሶሊኒ ደግሞ፣ እኔን ዴሞክራት አይደለም እያሉ የሚነቅፉና የሚንቁ ሁሉ፣ ተመልሰው እናከብርህ ! እናድንቅህ ! የሚሉበት ቀን ይመጣል በማለት ሲፎክር ቆይቶ ነበር።

ሙሶሊኒ እንደታየው፣ በጥር 30 ቀን 1933 ዓ.ም ሂትለር የተባለው ሌላው ትልቁ ዲክታተር ጀርመንን በሙሉ ሥልጣን በያዘ ጊዜ፣ ፈረንሣዮች ከፍተኛ ሥጋት ስለአደረባቸው፣ እንደዚያ ሲጠሉትና ሲዘልፉት የነበረውን የፋሽስት መሪ፣ ወዳጅ ማድረግና ግንኙነታቸውን ማሻሻል ግዴታ ሆነባቸው። « ... በሁለቱ አገሮቻችን መካከል ከጥንታዊው ዘመን ጀምሮ ሲያያዙ የመጡት የባሕልና የቅርስ፣ የሥልጣኔና የታሪክ፣ የዘርና የቋንቋ ግንኙነቶች እጅግ የዳበሩ በመሆናቸው፣ ተራርቀን መኖር እንደሌለብን ያስገድዱናል ... » በሚል አነጋገር፣ የፈረንሣይ ሬፑብሊክ መሪዎች ከፋሽስቱ ዲክታተር ጋር ወዳጅነት ለመመሥረት ፍላጐታቸውን ሲገልጹ፣ ሙሶሊኒ ደግሞ፣ « ... ቀድሞውንም ቢሆን የጠላቻሁንና የራቃችሁን እናንተ፣ አሁንም ለመቀራረብና በወዳጅነት አብሮ ለመሥራት የፈለጋችሁ እናንተ ስለሆናችሁ፣ የምንቀበላችሁ በጋለ የደስታ መንፈስ ነው ... » በማለት ደህና አድርጎ ተቀኘባቸው። ሆኖም ፈረንሣዮች በሂትለር ምክንያት ከሙሶሊኒ ጋር ወዳጅ መሆን ስለሚያስፈልጋቸው፣ የሚጠሉትንም ቢሆን በትዕግሥት ከመቀበል በስተቀር በዚያን ጊዜ ሌላ ምርጫ አልነበራቸውም።

በመሠረቱ ፈረንሣዮች፣ የመጀመሪያው የዓለም ጦርነት ሲፈጸም፣ የራሳቸውን ጥቅም ብቻ በማየት፣ በአንድ በኩል የጦር ጓደኛቸው ሆና የተሰለፈችውን ጣልያንን በብርቱ ሲያስቀይሙ፣ በሌላ በኩል ደግሞ ድል ባደረጉት በጀርመን ላይ የወሰዱት የቅጣት እርምጃ፣ ከልጅ ወደ ልጅ የሚተላለፍ ምሬትንና ጥላቻን አትርፎላቸዋል። እንደሚታወሰው፣ በዚህ በመጀመሪያው የዓለም ጦርነት ላይ፣ ፈረንሣይና እንግሊዝ፣ ጣልያን ከጐናቸው ሆና እንድትዋጋ ሲያደርጉ፣ ድሉ በሚገኝበት ጊዜ፣ ከጀርመን ላይ ከሚወርሱት የአፍሪካ ቅኝ ግዛት አገሮች ውስጥ ተካፋይ ትሆናለች ብለው የሰጡትን ቃል፣ በመጨረሻው ሳይፈጽሙት በመቅረታቸው፣ ጣልያኖቹ ብቻ ሳይሆኑ፣ የሌሎቹም የአውሮፓ ሕዝቦች እጅግ

አዝነውባቸዋል። በዚያን ጊዜ፣ ሙሶሊኒ፣ በጦር ሜዳ ዘምቶ የቆሰለ ከመሆኑም በላይ፣ በጋዜጠኝነቱ በጣልያን ሕዝብ ላይ የደረሰውን በደል እያፋፋመ በሚገልጽበት ጊዜ፣ ከእንግሊዞች ይልቅ በተለይ የፈረንሣዮችን ክፋትና ሸፍጥ በሰፊው ሲያወግዝ እንደነበረ ይታወሳል። በዚሁ በመጀመሪያው የዓለም ጦርነት ፍጻሜ ላይ፣ የጀርመንን ኃይል በመደምሰስ ግንባር ቀደምትነቱን ይዛለች የተባለችው ፈረንሣይ፣ በ1919 ዓ.ም በቬርሣይ (ፈረንሣይ አገር) በተደረገው የሰላም ስምምነት፣ ጀርመን ምንጊዜም ተመልሶ በጦር ኃይል እንዳያንሰራራ፣ በጥብቅ ቁጥጥር ተወጥሮ እንዲኖር ያደረገችበት ጭቆናና፣ በጦር ካሣ አከፋፈልም ረገድ የጣለችበት ጫና እጅግ ከሚገባ በላይ በመሆኑ፣ ሕዝቡ የተሰማው ኃዘንና ያሳደረው ቂም ወሰን አልነበረውም።

በአውሮፓ ላይ ስለ ፋሽዝምና ናዚ አነሣስ፣ ብዙዎቹ የፖለቲካ ሊቃውንቶች እንዳጠኑት፣ የመጀመሪያው የዓለም ጦርነት ድል አድራጊዎች የሆኑት የፈረንሣይና የእንግሊዝ መንግሥታት፣

1/ የጦር ጓደኛቸው ሆና ለተሰለፈችው ጣልያን የሰጧትን ቃል ባለመፈጸማቸው፣ በዴሞክራቶችና በሊበራሎች በሚመራው መንግሥት ላይ ያደረሱት የሞራልና የኢኮኖሚ ውድቀት፣ ለፋሽዝም መወለድና ሥልጣን መያዝ እጅግ አድርጐ የረዳ መሆኑን፣

2/ በቬርሣይ የሰላም ጉባኤ ሲደረግ፣ ድል በሆነው በጀርመን ላይ ያደረጉት የጭካኔ ቅጣትና የጦር ካሣ እንዲከፍል የወሰኑበት የግፍ ፍርድ፣ « ናሽናል ሶሲያሊዝም » (ናዚ) የተባለውን የአዶልፍ ሂትለርን ፓርቲ ሕዝቡ እንዲቀበለው ዕድል መስጠቱን፣

ተንትነው በማስረዳት፣ የፈረንሣይንና የእንግሊዝን መሪዎች አርቆ አለመመልከት ያወግዛሉ። የቀረው ቢቀር፣ ለጦር ካሣ እንዲከፍላቸው የጠየቁትን አንድ መቶ ሠላሳ ሁለት ሚሊያርድ በወርቅ የተያዘ ማርክ፣ የጀርመን ሕዝብ ለመክፈል በትንሹ አምሳ ዓመታት እንደሚፈጅበት እያወቁ፣ እስከዚህ መጨከንና መንግሥቱን ማስቃየት አልነበረባቸውም ይላሉ።

ይህንን ከባድ የሆነ የጦር ካሣ የጀርመን መንግሥት እንዲከፍላቸው ከፈረዱበት ከዐሥራ ሦስት ዓመታት በኋላ፣ አዶልፍ ሂትለር የናሽናል ሶሲያሊዝም ባንዲራውን አንግቦ የመንግሥቱን ሥልጣን ለመያዝ በተነሣ ጊዜ፣ የፕሮፓጋንዳው ሚኒስትሩ ዮሴፍ ጉበል፣ (Joseph Goebbels) ፈረንሣዮችና እንግሊዞች በጀርመን ላይ ስለሚያደርሱት በደል፣ በየአደባባዩ እየዞረ በዝርዝር በማስረዳቱ፣ በአጭር ጊዜ ውስጥ ሕዝቡ ምን ያህል እንደተማረከና ከናዚስቶች ጋር ለመሰለፍ እንደወሰነ፣ በግልጽ ታይቷል። ዶክተር ጉበል ለሕዝቡ ባደረገው ንግግር፣ « ... የፈረንሣይና የእንግሊዝ መሪዎች "የጦር ካሣ" ብለው የጫኑብንን ዕዳ ለመክፈል፣ የጀርመን ሕዝብ በድህነት እየተሰቃየ ለሚቀጥሉት ዐርባ ዓመታት እንዲኖር የሚያደርግ ብቻ ሳይሆን፣ ገና ባልተወለዱት ጀርመኖች ላይ፣ የሞት ቅጣት አዘጋጅቶ የሚጠብቃቸው ነው ... » ሲል የሕዝቡን ስሜት በጋለ መንፈስ ቀሰቀሰ። ስለዚህ፣ የጀርመን ሕዝብ ለናሽናል ሶሲያሊዝም ፓርቲ የድጋፍ ድምፁን ቢሰጥ፣

1ኛ/ ጀርመን፤ ከፈረንሣይና ከእንግሊዝ የግፍ ፍርድ ተላቅቃ፤ የጦር ካሣ የተባለውን ክፍያ እንደምታቆም፤

2ኛ/ ጀርመን፤ በግፈኞቹ ጠላቶቿ የተደረገውን የቬርሣይን ውል አልቀበልም ብላ፤ የራሷን ነፃነትና የወደፊት ሕይወት በሕዝቧ ፈቃድ እንደምትገነባ፤

3ኛ/ ጀርመን፤ በዓለም ላይ የነበራትን የተከበረ ቦታዋን እንደገና ለመያዝና፤ የሕዝቦቿን የኑሮ ዕድገት ከጣት ቁጥር በማይበልጡ ዓመታት ውስጥ ከከፍተኛ ደረጃ ላይ እንደምታደርስ፤

አስማምሮ የሚያቀርበው የዶክተር ጉበል ፕሮፓጋንዳ ሕዝቡን ስለአሳመነ፤ በጥቂት ጊዜ ውስጥ ለአዶልፍ ሂትለር መሪነትና ለናዚ ፓርቲው የሚጉርፈው ድጋፍ መላ ጀርመንን አጥለቀለቀው።

በዚህ አኳኋን በጥር 30 ቀን 1933 ዓ.ም፤ ሂትለር ቻንስለር (ጠቅላይ ሚኒስትር) ሆኖ መንግሥት ባቋቋመ ጊዜ፤ አንድ ቀን ሲመቸው ብድር ለመመለስ የመጀመሪያ ዒላማውን የሚያነጣጥረው ፓሪስ ላይ ነው ተብሎ ስለተገመተ፤ ፈረንሣይ ከዚህ አደጋ ለመዳን ብዙዎች ነገሮችን ማሰብና ማዘጋጀት ግዴታ ሆነባት። በነዚህ ወሰንተኞቿ በሆኑት በሁለት አገሮች ላይ የነገሡት ዲክታተሮች፤ አንድ ቀን ተባብረው ሊያጠቋት ቢነሡ፤ ፋሽስቱን ከበስተደቡቧ፤ ናዚውን ከበስተምሥራቋ፤ ሁለቱንም በአንድ ጊዜ ለመመከት ስለማትችል፤ በመጀመሪያ ከዱቼ ሙሶሊኒ መንግሥት ጋር ሰላም መመሥረትንና በወዳጅነት መተሳሰርን መረጠች። የፋሽስቱ መሪ፤ ምንም እንኳ ሊበራል ከሆኑት አገሮች ይልቅ፤ ከናዚስቱ መሪ ጋር የመጣጣምና የመቀራረብ መንፈስ ቢኖረውም፤ የሂትለር ወዳጅነት ለወደፊቱ ዘመን ካልሆነ በስተቀር፤ በዚያን ሰዓት ሌት ተቀን ለሚያልመው፤ ኢትዮጵያን ለመውረር በሚመለከተው ጉዳይ እንደማይጠቅመው ስለተረዳ፤ ከፈረንሣይ ጋር በቅድሚያ አንድ ዓይነት ስምምነት ማድረግ ይሻለኛል ብሎ ተነሣ።

ይህ በጣልያንና በፈረንሣይ መንግሥታት መካከል የሚደረገው ውል፤ አዲስ የወዳጅነት በር የሚከፍት ይሆናል ብለው ሁለቱም ወገኖች ስለአመኑበት፤ ፒየር ላቫል (PIERRE LAVAL) የተባለው የፈረንሣይ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር፤ በኦፊሲየል ግብዣ ሮም መጥቶ፤ ከፋሽስቱ መሪ ጋር ስምምነቱን እንዲፈራረም ተወሰነ። በዚህ ጊዜ የሁለቱ አገሮች የፖለቲካ መሪዎች ስለሚፈርሙት ስምምነት፤ በየበኩላቸው የነበራቸው አስተያየት የሚከተለው ነበር።

የፈረንሣይ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር መልዕክተኞቹን ይዞ ሮም ከመምጣቱ ከሁለት ሳምንታት በፊት፤ ሙሶሊኒ ለሼፍ ደ-ካቢኔው ለባሮን አሎይዚ (BARON ALOISI) በላከው መምሪያ፤ « ... ከፈረንሣይ መንግሥት ጋር በምፈርማቸው የወዳጅነት ስምምነቶች ላይ፤ ከሌሎቹ ጉዳዮች ሁሉ የበለጠ ቁም ነገር አድርጌ የምጠብቀው፤ ኢትዮጵያን የሚመለከተውን ክፍል ነው። በኢትዮጵያ ላይ ለምወስደው እርምጃ ፈረንሣዮች በይፋ ይደግፉኛል ብዬ ባላልምም፤ እጅግ ቢያንስ ተቀዋሚዎቼ ሆነው እንዳያስቸግሩኝ ቃል ይገቡልኛል ብዬ ሙሉ ተስፋ አደርጋለሁ። ይህ ብዙ ሲወራለት የኖረው የወዳጅነት ስምምነት፤ በምንፈልገው መልክ ከተፈጸመ፤ በኢትዮጵያ ጉዳይ እንቅፋት የሚሆኑብን ነገሮች ሁሉ ሊወገዱ ይችላሉ። ስለዚህ፤ ስምምነቶቹን እንዲያዘጋጁ የታዘዙት የጣልያንና የፈረንሣይ

ዲፕሎማቶች፣ ሥራቸውን በዚህ መምሪያ መሠረት እንዲያከናውኑ ማትጋት ብቻ ሳይሆን፣ ማሳመንም ያስፈልጋል። ስምምነቱም በጥር ወር (JANUARY 1935) መጀመሪያ ሳምንት ላይ እንዲፈረም እፈልጋለሁ ... » ሲል ዝርዝር ትዕዛዝ ሰጥቶታል።

ባሮን አሎይዚ የዱቼን መምሪያ ተከትሎ ስለሚዘጋጁት ስምምነቶች ከፈረንሣይ ዲፕሎማቶች ጋር ሲነጋገር፣ ሁለቱ አገሮች በሰሜንና በምሥራቅ አፍሪካ ባሏቸው ቅኝ ግዛቶቻቸው ላይ፣ እስከዛሬ የገጠሟቸውን ችግሮች ሁሉ በቅን መንፈስ ለማስወገድ ሲስማሙ፣ ስለ ኢትዮጵያ ጉዳይ ሙሶሊኒ የሚፈልገውን ለመቀበል የ-ኬ ዶርሰይ (QUAI-D'ORSAY) ዲፕሎማቶች የማይበገሩ ሆኑ። በዚህ ጊዜ ባሮን አሎይዚ፣ የሙሶሊኒ ልዩ ወዳጅ ለሆነው ለውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ለፒየር ላቫል ማመልከት ግዴታ ሆነበት።

ፒየር ላቫል፣ ለረዳቶቹ ቀጥታ ትዕዛዝ መስጠት አልፈለገም። የተሻለ ዘዴ መስሎ የታየው፣ ዋና ዋና የሆኑትን ረዳቶቹን ሰብስቦ፣ ፈረንሣይ ከፋሽስቱ መንግሥት ጋር ማድረግ ስለአስፈለጋት የወዳጅነት ስምምነት ምክንያቱን ከገለጸላቸው በኋላ፣ በዚህ ስምምነት ፈረንሣይ ከሙሶሊኒ ምን እንደምትጠይቅና፣ ሙሶሊኒም በበኩሉ ምን እርዳታ እንደሚፈልግ አስረድቶ፣ አስተያየታቸውን አጥንተው እንዲሰጡት ጠየቃቸው።

<u>ላቫል ለረዳቶቹ የገለጸላቸው ሐሳብ የሚከተለው ነበር።</u>

« ... ወደድንም ጠላንም፣ ዲክታተሩ በአውሮፓ አገሮች መካከል ትልቅ ቦታ ያለው መሆኑን አሳምኖናል። የጣልያንም ሕዝብ ከድህነት ኑሮው ተላቅቆ ወደ ተሻለ ሕይወት አምርቷል። የአገሩም ልማት በእርሻ ሆነ በኢንዱስትሪ እያደገ ሄዷል። የዲክታተር አስተዳደሩም ከጊዜ ወደ ጊዜ እየተሻሻለ፣ የሰብአዊነትን መልክ ማሳየት ጀምሯል። ዊንስተን ቸርችል በሮማ አደባባይ ሲናገር፣ « ... **በዚህ ዓለም የዕድገትና የሰው ልጅ ነፃነት እንቅፋት የሆኑትን ከሙኒስቶች፣ ሙሶሊኒ በረቀቀ ዘዴ ድራሻቸውን በማጥፋት ለአገሩ የተፋጠነ እርምጃ ለማስገኘት በመቻሉ፣ እኔ ጣልያን ብሆን የድጋፍ ድምጼን ለዱቼ ለመስጠት አላመነታም ነበር፣...** » እስከ ማለት ደርሷል። ሁላችሁም እንደምታውቁት፣ የታላቋ ብሪታንያ የፖለቲካ መሪዎች፣ በጣልያን አገር የፋሽስት መንግሥት መቋቋሙን በግልጽ ሳይቃወሙና የቀድሞ ግንኙነታቸውን በነበረው መልክ በመቀጠላቸው፣ በዛሬው ሰዓት በሙሶሊኒ ዘንድ ከእኛ እጅግ የተሻለ የወዳጅነት ቦታ ተሰጥቷቸዋል። እኛ ፈረንሣዮች ግን፣ ካለፉት ዐሥር ዓመታት ጀምሮ ሙሶሊኒን በፋሽስትነቱና በዲክታተርነቱ እየነቀፍን፣ ግንኙነታችንን አቀዝቅዘን መቆየታችን ስህተት ስለሆነ፣ ዛሬ ማረም እንዳለብን ተረድተናል። ያለፈውን እንዳለፈ ቆጥረን፣ አዲስ በምንዘረጋው የግንኙነት ጉዳና፣ ከሙሶሊኒ መንግሥት ጋር ለጋራ ጥቅማችን አብረን እንድንሠራ የጊዜያችን የፖለቲካ ሁኔታ አስገድዶናል። ከጥቂት ቀናት በኋላ፣ በእኔ የሚመራው የፈረንሣይ መልዕክተኞች ቡድን ወደ ሮም የሚጓዘው፣ ከሙሶሊኒ መንግሥት ጋር አዲስ የወዳጅነት በር በይፋ ለመክፈት ነው። **ይህንን አዲሱን ግንኙነት መርቀን ስንከፍት፣ እኛ ፈረንሣዮች ከሙሶሊኒ የምንፈልገውንና፣ የፋሽስቱም መሪ ከእኛ የሚጠይቀውን እርዳታ፣ መመዘንና ጥቅምና ጉዳቱን መለየት ይኖርብናል።** እንደምታውቁት በአሁኑ ሰዓት ለእኛ የሙሶሊኒ እርዳታ የሚያስፈልገን ለአንድ ትልቅ ጉዳይ ነው። ይኸውም፣ ባለፉት ሁለት ዓመታት ጀርመን ላይ በደረሰው

ለውጥ፤ የሂትለር አመጣጥና የሥልጣን አያያዝ ለእኛ ለፈረንሣዮች ብቻ ሳይሆን፤ በመላው የአውሮፓ ዴሞክራሲ አገሮች ላይ ትልቅ አደጋ የሚያስከትል ስለሆነ፤ ሂትለርንና የናዚ ፓርቲውን ለመቋቋም፤ የሙሶሊኒ እርዳታ የግዴታ ያስፈልገናል። እንደምታውቁት፤ ሂትለር ያለ ሙሶሊኒ ብቻውን የሚያልመውን ሁሉ መፈጸም አይችልም። ሂትለር፤ ሲቸግረው ወይም ሲጨንቀው፤ የሚሮጠው ሙሶሊኒ ዘንድ ነው። ስለዚህ፤ ሙሶሊኒን ከሂትለር ወዳጅነት ገንጥለን የኛ ብቻ እንዲሆን ካደረግነው፤ ሥጋታችን ይወገዳል። የምንፈልገውም ሰላም ይጠነክርልናል። እኔ እስከማውቀው ድረስ፤ ይህንን የምንጠይቀውን ሙሶሊኒ እንደሚቀበል ሙሉ እምነት አለኝ። ነገር ግን፤ እኛ ከሙሶሊኒ የምንጠይቀውን ካገኘን፤ ሙሶሊኒ ከእኛ **የሚፈልገውን በምን አኳኋን ልናረካው እንደምንችል በጥንቃቄ ማጥናት አለብን። የሙሶሊኒ ጥያቄ የሚከተለው ነው።**

አሁን በቅርቡ ወር ባልሞላ ጊዜ ውስጥ፤ ኢትዮጵያ የጣልያን ቅኝ ግዛት የሆነውን የሱማሌን ድንበር አልፋ "ወልወል" በተባለው ቦታ ላይ ከጣልያን ወታደሮች ጋር ባነሣቸው ጠብ ምክንያት፤ የብዙ ሰዎች ሕይወት አልፏል። ይህንንም፤ የሙሶሊኒ መንግሥት ለሊግ ኦፍ ኔሽን ሲያስታውቅ፤ ኢትዮጵያ ደግሞ በበኩሏ፤ ወሰን ጥሰው ተኩሱን የከፈቱት የጣልያን ወታደሮች ናቸው በማለት፤ ክስ አቅርባለች። ይህ ግጭት ከደረሰበት ቀን ጀምሮ፤ በጣልያን ሱማሌና በኢትዮጵያ ጠረፍ ላይ፤ የሁለቱ መንግሥታት ወታደሮች የሚለዋወጡት ተኩስ እስካሁን አልቆመም። ሙሶሊኒ በዚህ እጅግ ተበሳጭቶ ኢትዮጵያን ለመያዝና ቅኝ ግዛቱ አድርጐ ለማስተዳደር ቆርጦ ተነሥቷል። ለዚህም ሁለት ምክንያቶች ይሰጣል።

1ኛ/ የጣልያን ቅኝ ግዛቶች በሆኑት በኤርትራና በሱማሌ አገሮች ላይ፤ ኢትዮጵያ በየጊዜው ወሰን እየጣሰች በሕዝቡ ላይ የምትጥለው አደጋና የሚሞቱት ሰዎች እየበረከቱ በመሄዳቸው፤ ሰላም እንዲሰፍን የግዴታ ኢትዮጵያን መያዝ ያስፈልጋል።

2ኛ/ ፍጹም የሆነውን የፊውዳል አስተዳደር የምትከተለው ኢትዮጵያ፤ ያንን ሁሉ ያልተነኩ ሰፋፊ መሬቶችና የማዕድን ሀብት አንቃ ይዛ፤ ጐረቤቶቿ የሆኑትን አገሮች ሰላም እየነሣች ከምታስቸግር፤ የፋሽስት መንግሥት እያስተዳደራት፤ **በአገሩ ጥበት ምክንያት ተጨናንቆ የሚኖረው የጣልያን ሕዝብ ቢሰፍርበትና ቢያለማት፤ ለራሷ ዕድገትና የተሻለ ሕይወት ለማግኘት ይረዳታል።**

የሚል ነው።

እንግዲህ ! እነዚህን ምክንያቶች ተመርኩዞ፤ ሙሶሊኒ ኢትዮጵያን ለመያዝ እርምጃ ሲወስድ፤ ከፈረንሣይ መንግሥት የሚፈለገው ምንድን ነው ? ... ወደ ሮም ጉዞ ከመጀመሬ በፊት በልዩ መልዕክት እኔ እንዳውቀው ያደረገው፤ ከኢትዮጵያ ጋር ጦርነቱን በሚያካሂድበት ጊዜ፤

1ኛ/ **በዠኔቭ የመንግሥታት ማህበርና እንዲሁም በሌላው ዓለም አቀፍ አደባባይ ላይ <u>የፈረንሣይ መንግሥት በቀጥታ የኢትዮጵያ ደጋፊ ሆኖ እንዳያወግዘኝ፤</u>**



ፒየር ላቫል የፈረንሣይ ጠቅላይ ሚኒስትርና የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ከዲክታተሩ ከቤኒቶ ሙሶሊኒ ጋር ስለ ኢትዮጵያ ጉዳይ የሚያደርጉትን ስምምነት ሲመክሩ።
(እ.ኤ.አ ጥር 7 ቀን 1935 ዓ.ም)

2ኛ/ በመንግሥታት ማህበር በኩል የኢኮኖሚ ጭቆና ሆነ ወይም ሌላ ማናቸውም ቅጣት እንዳይወሰንብኝ፣ የፈረንሣይ መንግሥት በተቻለው እንዲረዳኝ፣

የሚል ነው።

ቀደም ብዬ እንደገለጽኩላችሁ፣ የጊዜያችን የፖለቲካ ሁኔታ፣ ከዲክታተሩ መሪ ጋር ወዳጅነት መመሥረትና የጋራ ጥቅማችንን በሚመለከት ጉዳይ ለመረዳዳት የሚያስችል ስምምነት ማድረግ፣ ጠቃሚ መሆኑን መንግሥታችን ያምንበታል። ነገር ግን ሙሶሊኒን ከሂትለር ወዳጅነት ርቀህ ከእኛ ጋር ሁን የምንለውን ሲቀበል፣ እሱ ደግሞ በበኩሉ ብዙ ችግር የፈጠረችብኝን ኢትዮጵያን ስይዝ፣ ቀጥታ ድጋፍ ስጡኝ ባልላችሁ እንኳ፣ ግንባር ቀደም ተቃዋሚዎቼ እንዳትሆኑ ቃል ስጡኝ የሚል ስለሆነ፣ እናንተ የሥራ ረዳቶቼ በዚህ ጉዳይ ላይ ለገጠመኝ ችግር አንድ ዓይነት ዘዴ በመፈለግ አጥንታችሁ እንድታቀርቡልኝ እጠይቃችኋለሁ ... » በማለት መምሪያውን ሰጠ።

ፒየር ላቫል በዚህ በሚፈራረመው የወዳጅነት ስምምነት፣ ሁለቱ አገሮች ስለሚተባበሩበት ጉዳይ ለረዳቶቹ በሰጠው ማብራሪያ እንደገለጸው፣ የሙሶሊኒን ጥያቄ ለመቀበል ምን ያህል ዝንባሌ እንዳለው አሰምቷል። ይህንንም ከግቡ ለማድረስ የታወቁት የፈረንሣይ ዲፕሎማቶች አጥንተው፣ ከሐሳቡ ጋር የሚስማማ አንድ ዓይነት ድጋፍ እንደሚያቀርቡለት በተስፋ ጠብቆ ነበር። ነገር ግን፣ የዲፕሎማሲው ሊቃውንቶች የአለቃቸውን ትዕዛዝ ተቀብለው ጥናት ቢያደርጉም፣ የፈረንሣይን የዴሞክራሲ አቋምና የነፃነት ዕምነት የሚያቃውስ የተዋረደ ሐሳብ በመስጠት፣ ፋሽስታዊ ዝንባሌ ያለውን የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ለማስደሰት አልፈለጉም። በዚህም መሠረት፣ ዲፕሎማቶቹ ተሰብስበው በማጥናት ያደረባቸውን ትክክለኛ አስተያየት እንደሚከተለው አቀረቡለት።

« ... በአሁኑ ሰዓት የሙሶሊኒና የሂትለር ወዳጅነት እየጋለ የሚሔድበት ምክንያት፣ ፈረንሣይና ታላቋ ብሪታንያ ተስማምተው፣ እነዚህን ሁለት ዲክታተሮች ከአውሮፓ ምድር ለማጥፋት እርምጃ ይወስዱ ይሆናል በሚል ሥጋት መሆኑን እናምንበታለን። እንደሚታወቀው፣ እነዚህ የጣልያንና የጀርመን ዲክታተሮች፣ በአንድ ዓይነት ዕምነትና በአንድ ዓይነት አስተሳሰብ ላይ የተመሠረቱ አይደሉም። የአውሮፓ መንግሥታትም በጥላቻና በጥርጣሬ ስለሚመለከቷቸው፣ አንድነታቸውንና ተደጋጋፊነታቸውን ለማሳየት ሲጥሩ ቢታዩም፣ ወደፊት ጊዜ አግኝተው ኃይላቸውና ዕድገታቸው በሚስፋፋበት ጊዜ፣ የዕምነታቸውና የአመራራቸው ልዩነት እየተራራቀ እንደሚሔድ አይጠረጠርም። ለዚህም እስካሁን እንደታየው፣ በጣልያን ላይ የሙሶሊኒ አመራርና ግብ፣ ከሂትለር ሕልምና እርምጃ ጋር እንደማይመሳሰል፣ እንኳንስ በጥልቀት ተመራማሪዎች ለሆኑት ለፖለቲካ ሰዎች ይቅርና፣ ለራሳቸው ለሁለቱ ዲክታተሮችም ቢሆን፣ በመካከላቸው ያለው ልዩነት እንዳልተሰወረባቸው ማመን ይቻላል።

የፈረንሣይ መንግሥት በሙሶሊኒ የምትመራውን ጣልያንን፣ ከሚያስፈልግ በላይ ርቃ ወይም ችላ ብላ ለብዙ ዓመታት ተቃዋሚ መስላ መታየቷ፣ ምንም አልጠቀማትም ተብሎ የሚሰጠው ትችት ከእውነት የራቀ አይደለም። ይሁን እንጂ፣ ያለፈውን ስሕተታችንን እናርማለን ብለን፣ ዛሬ ደግሞ የዴሞክራሲ ዕምነታችንን የሚያዛንፍና በተከበረው ታሪካችን ላይ ውርደትን የሚያስከትል ሌላ አዲስ ስህተት መጨመር የለብንም። ሙሶሊኒ ከሂትለር ጋር የጀመረውን ወደ

ጥፋት የሚያመራ ሩጫውን አቁሞ፤ ከፈረንሣይና ከታላቋ ብሪታንያ ጋር መስለፍ የሚችለው፤ « ... ኢትዮጵያን ቅኝ ለማድረግ በምወስደው እርምጃ በተለይ ፈረንሣይ ያልተቃወመችኝ እንደሆነ ነው ... » ሲል ያቀረበው የድፍረት ጥያቄ፤ መቸውንም ተቀባይነት ሊኖረው የማይችል ነው ብለን እናምናለን፡፡ ሙሶሊኒ ይህን ጥያቄ በተለይ ለፈረንሣይ የሚያቀርበው ለምንድን ነው? ... ሥልጣን ከያዘበት ከ1922 ዓ.ም ጀምሮ በወዳጅነት ያልተለዩትን እንግሊዞችን ለምን ተዋቸው? .... ምናልባት እንግሊዞች ከፈረንሣዮች የበለጠ፤ ለታናናሽ አገሮች ትክክለኛ ፍርድና መብት የሚቆሙ ስለሆኑ፤ ሐሳቤን አይቀበሉኝም በማለት ይሆን? ... እንደዚህም አስቦ ከሆነ፤ መሳሳቱን በምንወስደው እርምጃ ማስገንዘብ ይኖርብናል፡፡

የብዙ ሺህ ዓመታት ነፃነትና ታሪክ ያላትን አገር፤ የመንግሥታት ማህበር አባል ሆና በዓለም ነፃ ቤተሰቦች መካከል ቦታ የተሰጣትን አገር፤ ዛሬ በአቅሙ ተማምኖ ነፃነቷን ለመግፈፍና ቅኝ ግዛቱ ለማድረግ የሚነሣውን ዲክታተር፤ የፈረንሣይና የእንግሊዝ መንግሥታት ዝም ብለው ሊመለከቱት አይችሉም፡፡ ሲሆን፤ ጦራቸውን አንሥተው፤ የዚችን አገር ነፃነት ለመጠበቅ በዲክታተሩ ላይ እርምጃ መውሰድ ይገባቸዋል፡፡ ይህን ማድረግ ካልቻሉ ደግሞ፤ የመንግሥታት ማህበር የተመሠረተበትን ሕግ ተመርኩዘው በማናቸውም ጉዳና በአጥቂው ላይ ትክክለኛ ፍርድ እንዲሰጥ ማድረግ ግዴታቸው ይሆናል፡፡ ስለዚህ፤ ሲኞር ሙሶሊኒ በተለይ ሊገነዘበው የሚያስፈልገው፤ ፈረንሣይን የሚያህል፤ የዴሞክራሲ ምንጭ፤ የሕዝቦች ነፃነትና መብት አስከባሪ፤ የትክክለኛ ፍርድ ተሟጋች የሆነች አገር፤ እንደ ዲክታተር በዕብሪት ተነሥቶ የሊግ ኦፍ ኔሽን አባል የሆነችውን ኢትዮጵያን በጦር ኃይል ሲወር፤ ዓይኗን ሸፍና ጆሮዋን ደፍና ታሳልፋለች ብሎ መጠበቅ ከቶ የማይቻል መሆኑን ነው፡፡

ሙሶሊኒ ከጥቂት ቀናት በፊት በሮም አደባባይ ባደረገው ሰፊ ንግግር፤ « ... በመሬት ጥበት ምክንያት ተጨናንቆ የሚኖረው የጣልያን ሕዝብ፤ ለም የሆነ ሰፊ አገር አግኝቶ በጠንካራ ሠራተኛነቱና በታወቀ ሞያው፤ ከፍተኛ የልማት ውጤት እንደሚያስገኝ፤ እርግጠኞች ነን ... » ካለ በኋላ፤ « ... ፈረንሣይና እንግሊዝ በአፍሪካና በእስያ እነዚያን ሁሉ ሀብታም አገሮች በቅኝ ግዛት ይዘው ሲንደላቀቁ፤ ጣልያን እንደ ሱማሌና እንደ ሊቢያ የመሳሰሉትን የምድረ በዳና የበረሃ አገሮች ሰብሳቢ ሆና መገኘቷ እጅግ ያሳዝናል ... » ብሏል፡፡ በዚህ አነጋገር ምን ለማለት እንደተፈለገ፤ ለማናችንም የተሰወረ ስላልሆነ፤ ለጊዜው የጣልያን ሕዝብ ሳጋጠመው የኤኮኖሚ ችግር አንድ መፍትሔ ብንሰነዝርለት፤ ምናልባት ሲኞር ሙሶሊኒ ሐሳቡን ወደ ሰላም ለመመለስ፤ ይገፋፋው ይሆናል የሚል ተስፋ አድሮብናል፡፡

ይኸውም፤

- የኢትዮጵያ ነፃነት እንደተጠበቀ ሆኖ፣
- የንጉሠ ነገሥቱ የአስተዳደር ሥልጣን ሳይነካ፣
- በሊግ ኦፍ ኔሽን የበላይ ጠባቂነት፣

አንድ ትልቅ የጋራ የልማት ድርጅት ተቋቁሞ፣ እጅግ ሰፊ የሆነውን የአገሪቱን ጥሬ ሀብት በማልማት፣ ለኢትዮጵያውያኖችና ለጣልያኖች የጋራ ጥቅም እንዲውል፣ ሁለቱን መንግሥታት ለማስማማት ፈረንሣይ ብትጥርበት፣ የሚገኘው ውጤት በኤኮኖሚው መስክ ብቻ ሳይሆን፣ በፖለቲካም ረገድ የተከበረ መልካም ግምት ሊያስገኝ ይችላል ብለን እናስባለን፡፡

<u>ክቡር ሚኒስትር፣</u>

እንደሚያውቁት የፖለቲካ መሪዎችና ዲፕሎማቶች የአንድን አገር ችግር የሚያጠኑበት፣ ወይም የሚመለከቱበት፣ ተመሳሳይ የሆነ አስተሳሰብ የላቸውም፡፡ እኛም ረዳቶችዎ በጠየቁን መሠረት፣ አጥንተን ከዚህ በላይ ያቀረብንልዎ ሐሳብ፣ መሠረታዊ በሆነው በዲፕሎማሲ አስተሳሰብና ልማዳዊ ሆኖ የቆየውን የመንግሥታችንን የአሠራር ልምድ ተመርኩዘን ነው፡፡ በፖለቲካ መስክ የቀረበውን ችግር በምን መልክ ለመፍታት እንደሚቻል የእኛ የረዳቶችዎ ኤክስፔሪያንስ ምንም ዓይነት መድኃኒት ሊያገኝ ባለመቻሉ፣ እጅግ እናዝናለን ... » ሲሉ፣ ዲፕሎማቶቹ አስተያየታቸውን ደመደሙ፡፡

ፒየር ላቫል፣ ከዱቼ ሙሶሊኒ ጋር ለመወዳጀት ያለው ፍላጐት የጋለ ቢሆንም፣ ረዳቶቹ የጠየቃቸውን አጥንተው ምንም ማድረግ አይቻልም ብለው በሰጡት አስተያየት ቅሬታ አላደረበትም፡፡ ይልቁንም ሙሶሊኒ የጠየቀውን ድጋፍ መቀበል፣ ለፈረንሣይ ምን ያህል ውርደት መሆኑን ዲፕሎማቶቹ ደህና አድርገው ስለአሳመኑት፣ ኢትዮጵያን በሚመለከተው ጉዳይ፣ ከፋሽስቱ መሪ ጋር ብቻውን ተወያይቶ አንድ ዘዴ ለማግኘት ከመሞከር በስተቀር፣ በሰነድ የሚዘጋጅ ስምምነት ማድረግ እንደማይቻል ተገንዝቦታል፡፡ እንዲሁም የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ከሙሶሊኒ ጋር ስገጠመው ችግር አንድ ዓይነት መፍትሔ በመፈለግ፣ ኢትዮጵያንና ጣልያንን በኤኮኖሚ ልማት ለማስተሳሰር እንዲቻል፣ ዲፕሎማቶቹ ያቀረቡትን ሐሳብ፣ ፒየር ላቫል ጨልፎ ወስዶ፣ የራሱን ፍላጐት በማከል በተደረገው ስምምነት ላይ እንዴት እንደተጠቀመበት እናያለን፡፡

የሙሶሊኒ ሼፍ ደ-ካቢኔ ባሮን አሎይዚ፣ በየዕለቱ በሚመዘግበው ማስታወሻው ላይ እንደገለጸው፣ « ... ሙሶሊኒና ላቫል ለሚፈራረሙት የወዳጅነት ስምምነት፣ በአዘጋጅዎቹ በጣልያንና በፈረንሣይ ዲፕሎማቶች መካከል መግባባት ጠፍቶ ነበር፡፡ ምንም እንኳ፣ ሙሶሊኒ ወደ ኢትዮጵያ ለሚያደርገው ዘመቻ ፒየር ላቫል በቃል የሰጠውን ድጋፍ በዶክመንት ያረጋግጥለታል ተብሎ ባይጠበቅም፣ በሚዘጋጀው ስምምነት ውስጥ፣ ይህንን የድጋፍ መንፈስ የሚፈነጥቅ አንድ ዓይነት የሐሳብ አገላለጽ (ፎርሙላ) እንዲገኝ፣ በኤክስፐርቶቹ ደረጃ የተካሔዱት ጥናቶች ሁሉ ውጤት መስጠት አልቻሉም፡፡ ስለዚህ፣ ሁለቱ የፖለቲካ መሪዎች ላቫልና ሙሶሊኒ ሮም ላይ በቀጥታ በመነጋገር፣ መፍትሔውን እንዲያገኙለት ለእነሱ ከመተው በስተቀር፣ ሌላ መንገድ የለም ተብሎ ተወሰነ ... »* ብሏል፡፡ በዚህ አኳኋን፣ ፒየር ላቫል መልዕክተኞቹን ይዞ ወደ ሮም ሲመጣ፣ ከዱቼ ጋር

---

* BARON ALOISI JOURNAL 1935

በሚፈራረመው የወዳጅነት ውል ውስጥ፤ የኢትዮጵያ ጉዳይ በምን መልክ እንደሚገለጽ አልተወሰነም ነበር ማለት ነው።

ሙሶሊኒ ሥልጣን ከያዘበት ካለፉት ዐሥራ ሁለት ዓመታት ወዲህ፤ አንድ ብዙ ጊዜ የፈረንሳይ ጠቅላይ ሚኒስትርና የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር የሆነ የፖለቲካ መሪ፤ በኦፊሲየል ሮም የሚመጣው ለመጀመሪያ ጊዜ ስለሆነ፤ ሙሶሊኒ ራሱ ባቡር ጣቢያ ድረስ ሔዶ ለፒየር ላቫል ያደረገው አቀባበልና ያዘጋጀው መስተንግዶ ለአንድ የመንግሥት መሪ እንደሚደረግ የፕሮቶኮል ሥርዓት ነበር። የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩና መልዕክተኞቹ፤ እ.ኤ.አ ጥር 4 ቀን 1935 ዓ.ም ሮም ከደረሱበት ጊዜ ጀምሮ፤ ስምምነቱ እስከተፈረመበት ቀን ድረስ፤ የሁለቱ አገሮች ኤክስፐርቶች ዶክመንቶቹን ሲያዘጋጁ፤ ቀደም ሲል እንደተነገረው፤ ኢትዮጵያን ከሚመለከተው በስተቀር፤ በሌሎቹ ጉዳዮች ላይ ብዙ ችግር አላጋጠማቸውም ነበር። በስምምነቱ ውስጥ ለሚጠቀሰው የኢትዮጵያ ጉዳይ አንድ ዓይነት መንገድ ሊገኝለት የቻለው፤ ጥር 6 ቀን ማታ የፋርኔዝ ቤተመንግሥት (PALAIS - FARNEZE) በተባለው በሮም የፈረንሣይ አምባሳደር መኖሪያ ቤት፤ ስለ ዱቼ ክብር በተደረገው ታላቅ የራት ግብዣ ላይ፤ ሙሶሊኒና ላቫል ብቻቸውን በአንድ በተለየ ሳሎን ውስጥ በሰፊው ከተነጋገሩ በኋላ ነው። የዲክታተሩ ሼፍ ደ - ካቢኔ በማስታወሻው እንደጠቀሰው፤ « ... እ.ኤ.አ ጥር 6 ቀን በፈረንሣይ አምባሳደር መኖሪያ ቤት በተደረገው የራት ግብዣ ላይ፤ ሁለቱ ሰዎች (ሙሶሊኒና ላቫል) ብቻቸውን በቆይታ ተነጋግረው ሲጨርሱ፤ ክቡር ዱቼ የተሰማው የጋለ የደስታ መንፈስ፤ ከዚህ ቀደም ታይቶ የማይታወቅ ነበር ... » ብሏል። ይሁን እንጂ፤ ሁለቱ ሰዎች ምስክር በሌለበት ቦታ ብቻቸውን ተነጋግረው ከስምምነት የደረሱበትን ጉዳይ፤ በተፈራረሙት ሰነድ ላይ እንዲገለጽ አላደረጉም።

እ.ኤ.አ ጥር 7 ቀን 1935 ዓ.ም ከምሽቱ በአንድ ሰዓት ከዐርባ አምስት ደቂቃ ፓላሶ - ቬኔሲያ (PALAZZO - VENEZIA) በተባለው በክቡር ዱቼ ጽሕፈት ቤት፤ ሙሶሊኒና ላቫል በተፈራረሚቸው ስምምነቶች ውስጥ፤ "ብርቱ ምሥጢር" በሚለው ሰነድ ላይ፤ ስለ ኢትዮጵያ የተገለጹት ሁለት ጉዳዮች ብቻ ናቸው። እነዚህም፤ የመጀመሪያው የኢትዮጵያን ኢኮኖሚ በማልማት ጣልያን ስለምትጠቀምበት ጉዳይ ሲሆን፤ ሁለተኛው ደግሞ በስዊዝ ካናል በኩል ወደ ኢትዮጵያ የሚተላለፉትን የጦር መሣሪያዎችና የወታደር ትጥቆች ጂቡቲ ወደብ ላይ ለማገድ፤ ፈረንሳይ ስለምትወስደው እርምጃ ነበር።

እ.ኤ.አ ታህሣሥ 13 ቀን 1906 ዓ.ም ሦስቱ ኮሎኒያሊስቶች (ፈረንሣይ - እንግሊዝ - ጣልያን) በሎንዶን ተሰብስበው፤ በአፄ ምኒልክ ጀርባ በገዛ ሥልጣናቸው ኢትዮጵያን በሦስት ዞን በመከፈል፤ እያንዳንዳቸው በሚፈልጉት መንገድ የአገሪቱን ኢኮኖሚ እያለሙ ለየራሳቸው እንዲጠቀሙበት ስምምነት አድርገው እንደነበረ ይታወሳል። በዚያን ጊዜ፤ አባ-ዳኘው ምኒልክ የኮሎኒያሊስቶቹን ሐሳብ ኢትዮጵያ የማትቀበለው መሆኑን አስታውቀው ስለነበረ፤ በዚህ ምክንያት ይሁን ወይም በሌላ፤ የተደረገው ስምምነት በተግባር ሳይውል ለሐያ ዘጠኝ ዓመታት (29) ቆየ። ይህ ስምምነት ሳይሠራበት ለብዙ ዘመናት ቢቆይም፤ አሁን በ1935 ዓ.ም፤ የሙሶሊኒ መንግሥት ለእንግሊዝ የተደለደለውን ዞን ሳይነካ፤ የጣልያንንና አብዛኛውን የፈረንሣይ ድርሻ በአንድነት አጣምሮ በማልማት እንዲጠቀምበት፤ ፒየር ላቫል ያቀረበውን ሐሳብ ዱቼ ስለተቀበለው፤ በተፈራረሙት የምሥጢር ሰነድ ላይ የሚከተሉት ቃላቶች ሰፍረው ይገኛሉ።

1ኛ/ በ1906 ዓ.ም የሦስቱ ኮሎኒያሊስቶች፣ የእንግሊዝ፣ የፈረንሣይና፣ የጣልያን መንግሥታት ኢትዮጵያን በሦስት አውራጃዎች ከፍለው፣ ኤኮኖሚዋን እያለሙ ለመጠቀም ባደረጉት ስምምነት መሠረት፣ ፈረንሣይ ከጂቡቲ እስከ አዲስ አበባ በዘረጋችው የምድር ባቡር መስመር ላይ ከምታገኘው ጥቅም በስተቀር፣ ሌላውን የኤኮኖሚ መስክ በሙሉ ለጣልያን መልቀቋን፣

2ኛ/ የጣልያንና የፈረንሣይ መንግሥታት ለጋራ ጥቅማቸው እየተጋገዙ የሚሠሩ በመሆናቸው፣ ሁለቱ አገሮች በምሥራቅ አፍሪካ ባሏቸው የወደብ በሮች ላይ፣ እነሱ የማይፈቅዱት ማናቸውም የጦር መሣሪያዎች እንዳይተላለፉ ጥብቅ ቁጥጥር የሚያደርጉ መሆኑን፣ ... በዚህም መሠረት፣ ፈረንሣይ ቅኝ ግዛቷ በሆነው በጂቡቲ ወደብና እንዲሁም ከጂቡቲ እስከ አዲስ አበባ ባለው የምድር ባቡር መስመር፣ ምንም ዓይነት የጦር መሣሪያዎችና ወታደራዊ ትጥቆች ወደ ኢትዮጵያ እንዳይገቡ ለማገድ የፈረንሣይ መንግሥት መተባበሩን፣

የሁለቱ የፖለቲካ መሪዎች ስምምነት ገልጾታል፡፡

እንግዲህ ! ከዚህ በላይ እንደታየው፣ ሙሶሊኒ ከላቫል ጋር በተፈራረመው ውል ላይ፣ ዲክታተሩ ኢትዮጵያን ለመውረር በሚነሣበት ጊዜ፣ ፈረንሣይ እንደማትቃወመው ላቫል የሰጠው ቃል ባይገለጽም፣ በዚህ ጉዳይ የሁለቱ ሰዎች ስምምነት መኖሩ የተረጋገጠ ስለሆነ፣ ፈረንሣይ የጠላታችን የፋሽስቱ መሪ ግብረአበር ነች ከመባል ሊያድናት አይችልም፡፡ በተጨማሪም፣ ኢትዮጵያ ለነፃነቷ መከላከያ ከልዩ ልዩ አገሮች የገዛቻቸው የጦር መሣሪያዎች እንዳይደርሷት፣ ፈረንሣይ በጂቡቲ ወደብና በባቡሩ መስመር ላይ እገዳ ለማድረግ፣ ከፋሽስቱ መሪ ጋር ያደረገችው ስምምነት፣ ኢትዮጵያን ለመጉዳት ከዚህ የበለጠ ምን ማድረግ ይቻላት ነበር ? ብሎ መጠየቅ ያስፈልጋል፡፡

ሙሶሊኒና ላቫል በኢትዮጵያ ላይ ዶልተው የተስማሙበትን ጉዳይ ሸፍነው የያዙት ሁለቱ ብቻ ስለሆኑ፣ ምሥጢሩ ሳያፈተልክ ለዘለዓለሙ ተቀብሮ የሚኖር መስሏቸው ነበር፡፡ ነገር ግን፣ የእግዚአብሔር ተአምሩ ብዙ ስለሆነ፣ እነዚህ ከፉዎች በምሥጢር የተስማሙበትን ጉዳይ ከአንድ ዓመት በኋላ፣ ሁለቱም በየፊናቸው የተለያየ ትርጉም በመስጠት፣ አለመግባባት ላይ ደርሰው ሲጋለጡ ታዩ፡፡ ሙሶሊኒ ላቫልን፣ በሮም ስምምነታችን ላይ ወደ ኢትዮጵያ ለማደርገው ዘመቻ "ነፃ እጅ አለህ" (MAIN LIBRE) የሚል ቃል ሰጥተኸኛል ብሎ ሲሞግት፣ ላቫል ደግሞ በበኩሉ፣ "ነፃ እጅ" (MAIN LIBRE) አለህ ያልኩህ፣ ኢትዮጵያን በኤኮኖሚ ለማልማት እንድትችል ነው እንጂ፣ አገሪቱን በጦር ኃይል ለመውረር አይደለም፣ የሚል ከእውነት የራቀ የማጭበርበሪያ ትርጉም ለመስጠት ሞከረ፡፡ ከጥር 23 ቀን እስከ የካቲት 19 ቀን 1936 ዓ.ም ድረስ፣ ሙሶሊኒና ላቫል ያልተግባቡበትን ጉዳይ ደብዳቤዎች በመጻጻፍ ሲነታረኩ፣ ምሥጢራቸውም ተዘክዝኮ ስለወጣ፣ በአገራችን በኢትዮጵያ ላይ የዶለቱት ሁሉ ምን ያህል አሳዛኝ መሆኑን በይበልጥ ለመረዳት አስችሎናል፡፡ ፒየር ላቫል፣ አጭበርብሮ ራሱን ለማዳን ስለ ስምምነቱ የሰጠውን ትርጉም ስንመለከት፣ « ... ኢትዮጵያን ይዘህ በኤኮኖሚ ለማልማት ነፃ እጅ አለህ ... » ማለትና « ... ኢትዮጵያን ለመውረር ነፃ እጅ አለህ ... » የሚል



በሙሶሊኒ የተዘጋጀውን ስምምነት፤ የፈረንሣይ ውጭ ጉዳይ መሪ በፊርማው አፀደቀ።

(ሮም እ.ኤ.አ ጥር 7/1935 ዓ.ም)

"... የፋሽስቱ መንግሥት ኢትዮጵያን ለመውረር በሚያደርገው ጦርነት ነፃ መሆኑን፤ ፈረንሣይ ትስማማለች"

ፒየር ላቫል 7/01/1935

ቃል መስጠት፤ ምንም ልዩነት ስለሌለው፤ ዞሮ ዞሮ የፈረንሣይ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር በአገሩ ስም ሆኖ ለዱቼ ሙሶሊኒ የገባለት ቃል፤ የኢትዮጵያን ነፃነት የሚያስገፍፍ የከሀዲ ሥራ መሆኑን ሊያሻሽልለት እንደማይችል ለማንም ግልጽ ነው።

ፒየር ላቫል፤ በጥር 6 ቀን 1935 ዓ.ም ከቤኒቶ ሙሶሊኒ ጋር በምሥጢር ሲነጋገርና ሥልጣኑ የማይፈቅድለትን "ነፃ እጅ" የተባለውን ቸርነት ሲለግስ፤ ያለጥርጥር ሲኞር ዱቼ፤ መላ ኢትዮጵያን በአጭር ጊዜ ውስጥ ይዞ፤ ጦርነቱም በቶሎ ይቆማል ብሎ ስለአመነ፤ ጉዳዩ በመንግሥታት ማህበር ላይ ቀርቦ ከፍተኛ ሙግት የሚደረግበትና ፈረንሣይም ትክክለኛ አስተያየቷን እንድትሰጥ የምትጋለጥበት ሁኔታ ይፈጠራል ብሎ አላሰበም ነበር። በሌላ አነጋገር፤ ሙሶሊኒ ወልወል ላይ የደረሰውን ግጭት ሰበብ በማድረግ፤ ባለው ከፍተኛ የጦር ኃይል ሳይውል ሳያድር ኢትዮጵያን እጁ ካደረገ በኋላ፤ ለሊግ ኦፍ ኔሽን ክስ ቢቀርብበትም፤ የመንግሥታት ማህበር ባለቀለት ጉዳይ ጣልያንን የሚጐዳ ብዙ ነገር ማድረግ አይችልም ብሎ አስቧል ማለት ነው።

ነገር ግን፤ የሙሶሊኒ ጦር ላቫል እንደገመተው፤ እንኳንስ በጥቂት ሳምንታት ውስጥ መላ ኢትዮጵያን ለመያዝ ይቅርና፤ ጦርነቱን ለመጀመር እንኳ ከወልወል ግጭት በኋላ የዐሥር ወራት ጊዜ የሚያስፈልገው ሆነ። ከዚህም በላይ፤ ጥቅምት 3 ቀን 1935 ዓ.ም ጦርነቱን ከከፈተ በኋላ፤ የኢትዮጵያ የመከላከያ ኃይል ለሰባት ወራት መክቶ ስለያዘው፤ ፒየር ላቫል የሙሶሊኒን የድል አድራጊነት ደስታ ሳይካፈል፤ በጥር 23 ቀን 1936 ዓ.ም ኢትዮጵያ ከመሸነፏ ከዘጠና ቀናት በፊት፤ ለሰባት ወራት ይዞት ከነበረው ከጠቅላይ ሚኒስትርነቱ ሥልጣን ተሻረ። በዚህም መሠረት፤ ፈረንሣዩ ላቫል፤ ለፋሽስቱ ዱቼ ጥር 7 ቀን 1935 ዓ.ም የለገሰው "ነፃ እጅ" የተባለው ድጋፍ፤ ጊዜው ያለፈበት የማይሠራ ዕቃ ሆኖ ተቆጠረ። ይሁን እንጂ፤ ፒየር ላቫል መጀመሪያ በውጭ ጉዳይ ሚኒስትርነት፤ ቀጥሎ በጠቅላይ ሚኒስትርነት፤ በሥልጣን በቆየበት ከጥር 1935 ዓ.ም እስከ ጥር 1936 ዓ.ም ድረስ፤ ለአንድ ዓመት ያለማቋረጥ በኢትዮጵያና በጣልያን ጠብ ጉዳይ፤ በመንግሥታት ማህበር ላይ ለወዳጁ ለሙሶሊኒ ድጋፍ ለመስጠት ምን ያህል ያምታታና ይቀላምድ እንደነበረ ዝርዝሩን ወደፊት እናቀርበዋለን።*

* የጣልያን ጠቅላይ ሚኒስትር ቤኒቶ ሙሶሊኒ እና የፈረንሣይ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር (ኋላ ጠቅላይ ሚኒስትር) ፒየር ላቫል፤ በኢትዮጵያ ጉዳይ ያደረጉት ስምምነት የተገኘው፤
ሀ/ በፓሪስ Quai D'orsay የውጭ ጉዳይ ዲፕሎማቲክ አርሺብ፤
ለ/ በሮም ARCHIVO DIPLOMATICO AL FARNESINA (ውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር) ነው።

# ምዕራፍ ፬

## የመንግሥታት ማህበር ሽምግልና

እ.ኤ.አ ታህሣሥ 14 ቀን 1934 ዓ.ም ኢትዮጵያ ግዛቷ በሆነው "ወልወል" ላይ የፋሽስት ጦር ያደረሰባትን ጉዳት ለገኔቭ የመንግሥታት ማህበር ካመለከተች ከሦስት ቀናት በኋላ፤ የሙሶሊኒ መንግሥትም በበኩሉ ወልወል የተባለው አውራጃ የሚገኘው በጣልያን ሱማሌ ውስጥ መሆኑንና ታህሣሥ 5 ቀን ግጭቱንም የፈጠረው የኢትዮጵያ ጦር ነው በማለት ክስ ማቀረቡ ይታወሳል።

ሊግ ኦፍ ኔሽን (የመንግሥታት ማህበር) ከሁለቱ አባል መንግሥታት ከኢትዮጵያና ከጣሊያን በቅደም ተከተል የደረሰውን አቤቱታ፤ ምክር ቤቱ እንዲያየው ለጥር 19 ቀን ቀጠሮ ሲወስን፤ የፈረንሣይና የእንግሊዝ መልዕክተኞች ማህል ገብተው አንድ ሐሳብ አቀረቡ። ይኸውም፤ ኢትዮጵያና ጣልያን በ1928 ዓ.ም በተፈራረሙት የወዳጅነት ስምምነት በአንቀጽ 5 ላይ በተገለጸው መሠረት፤ በመካከላቸው የሚፈጠረውን ማናቸውንም ችግር መጀመሪያ በቀጥታ ከዚያም ካልተቻለ፤ ሽማግሌዎች መርጠው መነጋገር ስለሚገባቸው፤ በዚህ በኩል ያለው መፍትሔ ሳይሞከር፤ ጉዳዩ በሊግ ኦፍ ኔሽን ምክር ቤት ቀርቦ መታየት የለበትም የሚል ነው። ይህንን ሐሳብ ገና ከመጀመሪያው ኢትዮጵያ ጠይቃ አልቀበልም ብሎ ያስቸገረው የሙሶሊኒ መንግሥት ነበር። አሁን ግን፤ ሙሶሊኒ ጉዳዩን በጥሞና ሲያየው፤ በጥር 19 ቀን በመንግሥታት ማህበር ምክር ቤት ከኢትዮጵያ ጋር ሙግት ለመግጠም በሚገባ ያልተዘጋጀ ስለሆነና፤ ጊዜ ማግኘት ስለአስፈለገው፤ በወዳጆቹ በፈረንሣይና በእንግሊዝ መልዕክተኞች በኩል የሽምግልናውን መንገድ እቀበላለሁ ብሎ አስታወቀ። ፈረንሣይና እንግሊዝም፤ ሙሶሊኒ የጠየቀው እንዲፈጸም ከኢትዮጵያ መልዕክተኛ ጋር ተነጋግረው ከተስማሙ በኋላ፤ በሊግ ኦፍ ኔሽን ምክር ቤት ለጥር 19 ቀን እንዲታይ አጀንዳ የተያዘለት ጉዳይ ላልተወነ ጊዜ እንዲተላለፍ አደረጉ።

ኢትዮጵያና ጣልያን በ1928 ዓ.ም በተፈራረሙት የወዳጅነት ስምምነት መሠረት፤ ሁለቱ መንግሥታት ቀጥታ በዲፕሎማሲ ጉዳና በመነጋገር፤ ወይም በሚመርጧቸው ሽማግሌዎች አማካይነት፤ ጠባቸው ታይቶ መፍትሔ እንዲሰጡባቸው በአጀንዳ የተያዙት ጉዳዮች፤

1ኛ/ ወልወል የተባለው ግዛት የማን አገር እንደሆነ ለይቶ ማሳወቅ፣

2ኛ/ ታህሣሥ 5 ቀን 1934 ዓ.ም የወልወል ግጭት የተጀመረው ከማን ወገን እንደሆነ ጥፋተኛውን ማግኘት፣

3ኛ/ ለወደፊቱ ይህን የመሰለው ችግር እንዳይደርስ ምን እርምጃ መውሰድ እንደሚሻል፣

ሁለቱ መንግሥታት ከአንድ ስምምነት ላይ ለመድረስ እንዲችሉ ነበር።

ከዚህ በላይ በተገለጸው አኳኋን፣ ከፋሽስት መንግሥት ጋር ቢቻል በቀጥታ፣ ባይሆን ደግሞ በሽማግሌዎች አማካይነት ለመነጋገር፣ የቀረበላትን ጥያቄ ኢትዮጵያ የተቀበለችው በቅን መንፈስ ሲሆን፣ ቀደም ሲል እንደተነገረው ሙሶሊኒ የፈለገው ጊዜ ለማግኘት እንጂ፣ ከእንግዲህ ወዲህ በሁለቱ አገሮች መካከል ቀጥታ በሚደረግ ንግግር ሆነ ወይም በሽማግሌዎች አማካይነት ተወያይቶ ሰላም እንዲፈጠር የሚፈልግ ሆኖ አልነበረም።

በዚህም መሠረት ገና ንግግሩ ከመጀመሩ በፊት፣ ለጣልያን መልዕክተኞች ከሙሶሊኒ የተሰጠውን ትዕዛዝ፣ ኢትዮጵያ ስትመለከት የማትቀበለው ሆኖ ተገኘ። « ... ይኸውም፣ በሁለቱ አገሮች መካከል የደረሰውን ግጭት በሰላም ለመፍታት ንግግሩ ሊጀመር የሚችለው፣ ከሁሉ አስቀድሞ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መንግሥት የወልወል ግዛታችንን ደፍሮ በዜጐቻችን ላይ ላደረሰው አደጋ ካሣ እንዲከፍል የተወሰነበትን ሁለት መቶ ሺህ የማሪያ ቴሬዛ ብር፣ ኤርትራ ላይ በሚገኘው የጣልያን ባንክ ውስጥ ካስቀመጠ በኋላ ነው ... » ሲል ጥጋበኛው ፋሽስት የራሱን ውሳኔ አስታወቀ። በዚህ ብቻ አልቆመም። ከጥቂት ቀናት በኋላ ደግሞ፣ ሙሶሊኒ ለዜና ማሰራጫ ድርጅቶችና ጋዜጦች በሰጠው መግለጫ፣ « ... ኢትዮጵያ ከእኛ ጋር ስለ ዕርቅ ጉዳይ ለመነጋገር የምትችለው፣ የተወሰነባትን ካሣ አስቀድማ በመክፈል ብቻ ሳይሆን፣ በወልወል ላይ ለደረሰው አደጋ ጥፋተኛ መሆኗን አምና ታላቁን የፋሽስት መንግሥት በይፋ ይቅርታ ስትጠይቅ ነው ... » የሚል የዕብሪት ሐሳብ ጨመረበት።

የፈረንሣይና የእንግሊዝ መልዕክተኞች፣ ፒየር ላቫልና አንቶኒ ኤደን ተመካክረው፣ ሰላምን ለመመለስ ሲባል ይህ ሙሶሊኒ የጠየቀው ሁለት መቶ ሺህ ዶላር በስዊስ ባንክ ተቀማጭ ቢደረግና ለግጭቱም ይቅርታው በአንድ የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ቃል አቀባይ ቢገለጽ አይሻልም ወይ ሲሉ፣ በገኔቭ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር የሆኑትን ፊታውራሪ ተክለሐዋርያትን ለመኗቸው። የታወቁት ተክለሐዋርያት ለቀረበላቸው ጥያቄ መልሱን ለመስጠት ንጉሠ ነገሥታቸውን ማማከር አላስፈለጋቸውም። « ... ኢትዮጵያ ሞትን የምትመርጠው ከነክብሯ ስለሆነ፣ ካሣውንም አትከፍልም። ይቅርታም አትጠይቅም። ሞትንም በጀግንነት ከመቀበሏ በፊት ወደ መንግሥታት ማህበር እንደገና መጥታ ትክክለኛ ፍርድ ትጠይቃለች ... » ብለው ወዲያውኑ መለሱላቸው።

ሙሶሊኒ ለሙግትና ለጦር የሚያደርገውን ዝግጅት ለማጠናቀቅ ጊዜ ስለሚያስፈልገው፣ ነገሩን ለማጓተት « ... የሁለቱ መንግሥታት እንደራሴዎች ቀጥታ ሲነጋገሩ መግባባት ስላልተገኘ፣ በስምምነታችን አንቀጽ 5 መሠረት ሽማግሌዎች መርጠን ጉዳያችን ቢታይ ይሻላል ... » አለ። ባሮን አሎይዚ የሙሶሊኒ ዋና መልዕክተኛ ይህን ሐሳብ ሲያቀርብ፣ ፊታውራሪ ተክለሐዋርያት የኢትዮጵያ መልዕክተኛ ተገቢውን መልስ ለመስጠት አልዘገዩም። « ቀድሞውንስ ቢሆን ገና ከጠዋቱ በወልወል ግጭት ማግስት፣ ጉዳያችን በሽማግሌዎች ይታይልን ብላ ደጋግማ ስታመለክት "እምቢ"! የተባለችው ኢትዮጵያ አልነበረችም ወይ ? የሚል ጥያቄ ካቀረቡ በኋላ፣ « ... ወዳጃችንና አሳቢያችን የሆነው የጣልያን መንግሥት የሚነቃው፣ ኢትዮጵያ ከተናገረች ከብዙ ወራት በኋላ ቢሆንም፣ ሐሳባችንን ተቀብሎ በመምጣቱ እንኳን ደህና መጣህ ! እንለዋለን › በሚል ቃል



ከወልወል ግጭት በኋላ፤ የመንግሥታት ማህበር በኢትዮጵያ እና በጣልያን መንግሥታት የቀረበውን ክስ ሲመረምር፤

ኢትዮጵያ ከሰው ሁሉ ቀድማ የጠየቀችውን የሽምግልና አሠራር ዛሬም ተከትላ ለመፈጸም የተዘጋጀች መሆኗን አስታወቀ።

ይሁን እንጂ፤ ቀደም ሲል ተደጋግሞ እንደተገለጸው ሲኞር ዱቼ ከኢትዮጵያ ጋር የፈጠረው የወልወል ጠብ በሰላም ጉዳና መፍትሔ እንዲያገኝ ስለማይፈልግ፤ እሱ ራሱ በጠየቀው መሠረት፤ በሊግ ኦፍ ኔሽን የተወሰነው የሽማግሌዎች ዳኝነት ሥራ እንዲዘገይ አደረገ። በኢትዮጵያ በኩል የሚያስፈልጉት ሁለት ሽማግሌዎች፤

1ኛ/ ሚስተር ደ-ላ ፕራዴል (DE LAPRADELLE) የተባለ በፓሪስ ዩኒቨርሲቲ የሕግ አስተማሪ የሆነ ፈረንሣዊ፣

2ኛ/ ሚስተር ፒትማን ፖተር (MR. PITTMAN POTTER) የተባለ በገኔቭ የኢንተርናሽናል ኢንስቲቱት መምህር የሆነ አሜሪካዊ፤ በመጋቢት ወር 1935 ዓ.ም ተመርጠው ሥራቸውን ለመጀመር ሲጠባበቁ፤ የዱቼ ሙሶሊኒ ዳኞች እስከ ግንቦት ወር 1935 ዓ.ም ድረስ ሳይሠየሙ ቀሩ።

እንግዲህ! የፋሽስት መንግሥት ከኢትዮጵያ ጋር ባለው ስምምነት መሠረት በቀጥታ ወይም በሽማግሌዎች አማካይነት እነጋገራለሁ ብሎ፤ በጥር 19 ቀን 1935 ዓ.ም በመንግሥታት ማህበር ምክር ቤት የተያዘውን ቀጠሮ ላልተወሰነ ጊዜ እንዲተላለፍ ካስደረገ በኋላ፤ በየጊዜው የተለያየ ምክንያት እየሰጠ፤ ንግግሩን ለመቀጠል ፈቃደኛ ሳይሆን፤ በበኩሉ የሚያስፈልጉትንም ሽማግሌዎች ሳይመርጥ፤ ለአራት ወራት አስተኝቶ አቆየው። ኢትዮጵያ ግን፤ ቢያንስ በየሁለቱ ሳምንታት አንድ ጊዜ፤

አንደኛ/ በሁለቱ አገሮች መካከል የሚጠበቀው የሰላም ንግግር አለመጀመሩንና፤ ከጣልያን በኩል የሚመደቡትም ሽማግሌዎች አለመሠየማቸውን፣

ሁለተኛ/ ከጣልያን አገር ወደ ኤርትራና ወደ ሱማሌ በየዕለቱ የሚላከው የፋሽስት ጦር ኃይል መጠኑ ሊገመት ከማይቻል በላይ ስለሆነ፤ በኢትዮጵያ ላይ የሚዘጋጀው አደጋ ምን ያህል አሳሳቢ መሆኑን በማየት፤ የመንግሥታት ማህበር ደንብ በሚያዘው በአንቀጽ 15 መሠረት አስፈላጊው እርምጃ እንዲወሰድ፤

ደጋግማ ከማመልከት አላቋረጠችም ነበር። ነገር ግን፤ የመንግሥታት ማህበር ዋና ጸሐፊ ዮሴፍ አቬኖል የፋሽስቶች የቅርብ ወዳጅ በመሆኑ፤ ከአዲስ አበባ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ብላቴን ጌታ ኅሩይ ወልደሥላሴ፤ እያከታተሉ የሚልኳቸውን የአቤቱታ ቴሌግራሞች ሁሉ፤ የመንግሥታቱ እንደራሴዎች እንዲያውቁት በማድረግ ፋንታ፤ ከሁሉ አስቀድሞ የሙሶሊኒ ወኪል አስተያየት እስከሚሰጥበት ጊዜ ድረስ እየደበቀ በመያዝ፤ ኢትዮጵያን የሚጐዳ ሥራ ሲፈጽም ቆየ። ለምሳሌ፤ ከጥር 19 ቀን 1935 ዓ.ም ወዲህ፤ የመንግሥታት ማህበር ምክር ቤት በመጋቢት 16 እና በሚያዝያ 15 ቀን 1935 ዓ.ም ሁለት ጊዜ ስብሰባውን አካሂዶ እንደነበረ ታውቋል። በእነዚሁ ጊዜያቶች ውስጥ ኢትዮጵያ አከታትላ ያቀረበቻቸውን አቤቱታዎች፤ የሊግ ኦፍ ኔሽን ዋና ጸሐፊ ፈረንሣዩ ሙሴ ዮሴፍ አቬኖል፤ ምክር

ቤቱ እንዲነጋገርበት ሳያደርግ፣ እስከ ግንቦት 1935 ዓ.ም ድረስ አቆየው። በመጨረሻው፣ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ለአምሳ ስድስቱ የመንግሥታት እንደራሴዎች በሙሉ በስማቸው ፈርመው፣ ግንቦት 20 ቀን 1935 ዓ.ም በላኩት ቴሌግራም፣

1ኛ/ በወልወል ጉዳይ ኢትዮጵያ ሽማግሌዎቿን መርጣ ካለፉት ሦስት ወራት ጀምሮ ስትጠብቅ፣ የጣልያን መንግሥት በየጊዜው ልዩ ልዩ ምክንያት እየፈጠረ የበኩሉን ባለመፈጸሙ፣ እስካሁን ንግግሩ አለመጀመሩን፣

2ኛ/ በኢትዮጵያ ወሰን ላይ በኤርትራና በሱማሌ በኩል የፋሽስት መንግሥት የሚያስፍረው ጦር ከዕለት ወደ ዕለት እየጨመረ መሄዱን፣

አጠንክረው ካመለከቱ በኋላ፣ በመንግሥታት ማህበር ደንብ አንቀጽ 15 መሠረት፣ ከሁለቱ አገሮች (ከጣልያንና ከኢትዮጵያ) ነፃ የሆነ ኮሚሽን ተቋቁሞ፣ በኤርትራና በሱማሌ ወሰናችን ላይ ያለውን ሁኔታ እንዲመረምርና ራፖሩን በቀጥታ ለሊግ ኦፍ ኔሽን እንዲያቀርብ፣ እጅግ አስፈላጊ መሆኑን አጥብቀው አሳሰቡ።

ይህንን ለመላው የመንግሥታት እንደራሴዎች የተላከውን የንጉሠ ነገሥቱን አቤቱታ፣ ሙሴ አቬኖል እንደሌላው ጊዜ ሸፋፍኖ ለመቅበር ስላልተመቸው፣ ሳይወድ በግድ እ.ኤ.አ ግንቦት 25 ቀን 1935 ዓ.ም በተደረገው የምክር ቤቱ መደበኛ ስብሰባ ላይ ቀርቦ እንዲታይ አደረገ። የሚያሳዝነው፣ የምክር ቤቱም አባሎች፣ ከዋናው ጸሐፊ የተሻሉ ሆነው አለመገኘታቸው ነው። የቀዳማዊ ኃይለሥላሴን አቤቱታ ከተመለከቱ በኋላ በሰጡት ውሳኔ፣ « ... ኢትዮጵያና ጣልያን በመካከላቸው የተፈጠረውን ግጭት በቀጥታ ተነጋግረው መጨረስ ስላልቻሉ፣ ሁለቱ መንግሥታት በሚመርጧቸው ሽማግሌዎች አማካይነት ጉዳያቸው ተጠንቶ በሚቀጥሉት ሦስት ወራት ውስጥ መፍትሔ እንዲቀርብበት ምክር ቤቱ ያሳስባል ... » የሚል አንካሳ መግለጫ አውጥተው ተለያዩ። ከዚህ ውጭ ግን ትልቁን አሳሳቢ ጉዳይ፣ በኤርትራና በሱማሌ ወሰን ላይ ስለሚከማቸው የፋሽስት ጦር ንጉሠ ነገሥቱ ያቀረቡትን አቤቱታ፣ የምክር ቤቱ አባሎች እርምጃ ሳይወስዱበት በዝምታ አለፉት።

የኢትዮጵያ መልዕክተኛ ፊታውራሪ ተክለሐዋርያት፣ በምክር ቤቱ አሠራር እጅግ አዝነው፣ የኢትዮጵያን ትልቁን አቤቱታ በቸልታ ያሳለፋችሁበት ምክንያት ምንድን ነው ? ብለው ሲጠይቁ፣ የተሰጣቸው መልስ የበለጠ የሚያሳዝን ሆነባቸው። ይኸውም፣ የሙሶሊኒ ዋና መልዕክተኛ ባሮን አሉይዚ ተጠይቆ ለምክር ቤቱ እንዳስረዳው፣ « ... ወደ ኤርትራና ወደ ሱማሌ ግዛታችን ጦር ለመላክ የተገደድነው፣ ኢትዮጵያ አድፍጣ አደጋ ለመጣል እንደምትዘጋጅብን መረጃ ስለደረሰን፣ ለመከላከያ መሰናዳት ስለአለብን ነው እንጂ፣ እኛ ከኢትዮጵያ ጋር ጦርነት ፈልገን አይደለም። ጦርነት ማድረግ የሚያስፈልገን ቢሆን ኖሮ፣ በሁለቱ አገሮቻችን መካከል ለደረሰው ግጭት፣ ሽማግሌዎች ተመርጠው ጉዳያችን እንዲታይልን መድከም አልነበረብንም ... » ሲል የዋስትና ቃል በመስጠቱ ነው ተባለ።

የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ዋና መልዕክተኛ፣ ምክር ቤቱ ያሳለፈው ውሳኔ ተገቢ አለመሆኑን ለማስረዳት ብዙ ጥረት አድርገዋል። ለዚህም ማስገንዘቢያ እንዲሆን

ያቀረቡትን ተረትና ምሳሌ ለመረዳት የምክር ቤቱ አባሎች ሳይቸገሩበት አልቀሩም። ፊታውራሪ ተክለሐዋርያት ሐሳባቸውን ለመግለጽ የሞከሩት በሚከተለው አኳኋን ነበር። « ... በአገሬ በኢትዮጵያ የሚነገር አንድ ተረት አለ። ውሃ ሰውን ሲወስድ እያሳሳቀ ነው ይባላል። የዚህን ምሳሌ በእናንተ በአውሮፓውያኖች አስተሳሰብ በትክክል መተርጐም ባልችልም፣ ተመሳሳዩን ሁኔታ ከዚህ ጋር አያይዤ ስነግራችሁ፣ ያለጥርጥር የተረቱ ትክክለኛው ምሥጢር ምን መሆኑን ልትረዱት ትችላላችሁ። በእኔ አስተሳሰብ ውሃ ሰውን ሲወስድ እያሳሳቀ (ወይም እያታለለ) ነው የተባለውን ምሳሌ የምጠቀመው፣ በአሁኑ ሰዓት የፋሽስት መንግሥት የአገሬን ነፃነት ለመግፈፍ ጉዞውን የጀመረው፣ እናንተን የዓለም መንግሥታት ዳኞችን እያታለለና እያስፈራራ መሆኑን በግልጽ ስለአየሁት ነው።

የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት፣ የፋሽስት መንግሥት በአገራችን ወሰኖች ላይ ያሰፈረው ጦር ምን ያህል አሥጊ መሆኑን በማስረዳት፣ በሊግ አፍ ኔሽን ደንብ መሠረት ገለልተኞች የሆኑ ዳኞች ወደ ሥፍራው ተልከው ይመርምሩልኝ ብለው ሲያመለክቱ፣ እናንተ የምክር ቤቱ አባሎች የምትሰጧቸው መልስ፣ ከባላጋራቸው ከባሮን አሎይዚ የተነገራችሁን የሐሰትና የማታለያ ፕሮፓጋንዳ ሆኖ ሲታይ፣ ማንን አያስገርምም ? ማንንስ አያሳዝንም ? .... ዳኝነታችሁ የሚመሠረተው፣ ከጉልበተኛው ወገን በሚሰጠው አስተያየት ላይ ከሆነ፣ የእኛ የደካሞችና የድሆች አገሮች ማህበርተኛችሁ ሆነን ወንበር መያዝ ለምን እንደሚያስፈልግ ? ጥቅሙም ለማን እንደሆነ ? ወደፊት በሰፊው አጥንተን መነጋገር እንደሚኖርብን ማመን አለብን። ለዛሬው ግን፣ እኔ ለጥቃት ዝግጅት የሚደረግላት አገር እንደራሴ የሆንኩት ሰው ከፊታችሁ ቀርቤ፣ ውሳኔያችሁ ትክክል አይደለም ብዬ ስናገር እንደማይጥማችሁ፣ ኃዘኔ መሪር መሆኑን ስገልጽ እንደማይሰማችሁ፣ በሚገባ የተረዳሁት ስለሆነ፣ ይህን ፊት ለፊት የተጋለጠ ስሕተታችሁን ለማረም ትሞክራላችሁ ብዬ ተስፋ አላደርግም።

..... ሆኖም የፋሽስት መንግሥት እንደራሴ ባሮን አሎይዚ የነገራችሁ ሁሉ፣ ምን ያህል የማታለያና የሐሰት ቃል መሆኑን ለመረዳት የምትችሉበት ጊዜ ሩቅ እንደማይሆን ላረጋግጥላችሁ እወዳለሁ። በተጨማሪም፣ በኢትዮጵያ ወሰኖች ላይ፣ በሰሜን በኤርትራ፣ በደቡብ በሱማሊያ፣ የፋሽስት መንግሥት ከግማሽ ሚሊዮን በላይ የሆነውን ተዋጊ ጦር ያሰፈረው፣ ኢትዮጵያን ለመውረርና ቅኝ ግዛቱ ለማድረግ ብቻ እንጂ፣ ሌላ ምንም ምክንያት እንደሌለው፣ ብታምኑኝም ባታምኑኝም፣ ሳላስገነዝባችሁ ከፊታችሁ መሰናበት አልፈልግም። ይህም በዛሬው ዕለት ያደረጋችሁት ውሳኔ፣ ኢትዮጵያ ካቀረበችላችሁ አቤቱታና የፋሽስቱ እንደራሴ ከሰጣችሁ መምሪያ ጋር ተያይዞ፣ በሊግ አፍ ኔሽን መዝገብ ላይ እንዲሰፍር፣ ክቡር ዋና ጸሐፊውን አጥብቄ የምጠይቀው፣ የዚህ ምክር ቤት አስተያየትና ውሳኔ በምን አኳኋን ይካሄድ እንደነበረ፣ ታሪኩ ለወደፊቱ ዘመን ትልቅ ትምህርት የሚሰጥ ይሆናል ብዬ በማሰብ ነው ... »

ከዚህ በላይ እንደታየው፣ ተክለሐዋርያት ባደረጉት ንግግር፣ የመንግሥታት ማህበር ምክር ቤት በአሠራሩ የፍርድ ሚዛን የሌለው መሆኑን እየተነተኑ በማስረዳት ቢሟገቱም፣ አድማጭ አግኝተው፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በጣልያን ቅኝ ግዛቶችና በኢትዮጵያ ወሰን ላይ መርማሪ ኮሚሽን ተልኮ እንዲታይላቸው፣ ያቀረቡትን ማመልከቻ ለማስፈጸም አልቻሉም። ይልቁንም፣ የኢትዮጵያ መልዕክተኛ ባደረጉት ንግግር፣ « ... ከፋሽስት መንግሥት የተሰጣችሁን መምሪያ ተከትላችሁ



ፊታውራሪ ተክለሐዋርያት ተክለማርያም፤ በመንግሥታት ማህበር፤
የኢትዮጵያ ዋና መልዕክተኛ፤

ያደረጋችሁት ውሳኔ ትክክል አይደለም ... » በማለት ምክር ቤቱን ስለዘለፉ፤ ጉዳዩ በዲሲፕሊን መታየት አለበት ብሎ፤ ዋናው ጸሐፊው ተነሥቶ ነበር። ነገር ግን፤ አብዛኛዎቹ የምክር ቤቱ አባላት፤ የአንድ መንግሥት እንደራሴ፤ በሰጠነው ውሳኔ ተበሳጭቶ ምሬቱን ስለገለጸ፤ ምን ዓይነት ዲሲፕሊን ትጠይቃለህ ? በማለት ስለአቃለሉበት፤ የሴፍ አቬኖል በሐሳቡ ለመግፋት ሳይችል ቀረ። በመሠረቱ፤ ተክለሐዋርያት ደህና አድርገው እንደአስረዱት፤ የመንግሥታት ማህበር ምክር ቤት በአባል አገሮች መካከል የሚፈጠረውን ችግር ለመፍታት የሚወስደው እርምጃ፤ የኃይለኛውን ወገን አስተያየት እየተመረኮዘ ስለሆነ፤ በድሆችና በደካሞች መንግሥታት ላይ የሚፈጽመው በደል፤ እጅግ አሳዛኝነቱ የሚካድ አልነበረም። በዚህ ሁኔታ፤ በኢትዮጵያና በጣልያን መካከል ለተነሣው ግጭት፤ የመንግሥታት ማህበር ከጥር 19 ቀን ጀምሮ እስከዚሁ እስከ ግንቦት 25 ቀን 1935 ዓ.ም ድረስ ያደረገውን ሁሉ ፊታውራሪ ተክለሐዋርያት ከተመለከቱ በኋላ፤ ከእንግዲህ ወዲህ፤ ኢትዮጵያ ከዤኔቭ ተገቢውን ፍርድ ማግኘት እንደማትችል ተስፋ ቆርጠው መታየታቸው ትክክል መሆኑን መገንዘብ ይቻላል። ንጉሠ ነገሥቱ ግን፤ ከመንግሥታት ማህበር ሳይጋጩ፤ ፍርድ ለማግኘት እስከመጨረሻው ሰዓት ድረስ በትዕግሥት መጠበቅን ስለመረጡ፤ የኢትዮጵያ መልዕክተኛም፤ ይህንኑ መምሪያ ከመከተል በስተቀር ሌላ መንገድ አልነበራቸውም።

እንግዲህ ! እንደሚታወሰው በግንቦት 25 ቀን 1935 ዓ.ም፤ የመንግሥታት ማህበር ምክር ቤት ባወጣው መግለጫ፤ ጣልያንና ኢትዮጵያ በመካከላቸው የተፈጠረውን ጠብ፤ በሚመርጧቸው ሽማግሌዎች አማካይነት ተነጋግረው፤ በሚቀጥሉት ሦስት ወራቶች ውስጥ እንዲያቀርቡልን የሚል ነው። ለዚህ ጉዳይ ኢትዮጵያ ገና ከሁለት ወራት በፊት ስምምነቱ የሚያዘውን በመከተል፤ በመጋቢት ወር 1935 ዓ.ም የታወቁ ሁለት ሽማግሌዎች፤ አንድ ፈረንሣዊና አንድ አሜሪካዊ መርጣ ስትጠባበቅ፤ ዱቼ ሙሶሊኒ ከሦስት ወራት በላይ ዘግይቶ፤ የራሱን የቅኝ ግዛት ጉዳይ ሚኒስቴር ባልደረቦች የሆኑትን ሁለት ሰዎች ለሽምግልናው ሥራ ሠይሞ አቀረበ። በደንቡ መሠረት፤ ለዳኝነቱ የሚመረጡት ሰዎች፤ በሁለቱ አገሮች መካከል ምንም ዓይነት የተሳሰረ ጥቅም የሌላቸውና ገለልተኞች መሆን ሲገባቸው፤ የሙሶሊኒ መንግሥት፤ እንዴት የራሱን ዜጎች፤ ያውም የቅኝ ግዛት ሚኒስቴሩ ባልደረቦች የሆኑትን ለዳኝነት መርጦ ያቀርባል ? .... ተብሎ ሲጠየቅ፤ የተሰጠው መልስ፤ « ... ኢትዮጵያም የራሷን ሰዎች መርጣ ማቅረብ ትችል ነበር ... » የሚል ሆነ። ኢትዮጵያ ከጥንት ሲያያዝ የመጣ ጨዋነትና በጎ ምግባር ስለአላት፤ በኢንተርናሽናል ሸንጐ ላይ ለሚታይ ዳኝነት የራሷን ዜጐች መርጣ ፍርድ ይታይልኝ አትልም። ሙሶሊኒ ግን፤ በማን አለብኝና በዕብሪት መንፈስ የተወጠረ ስለሆነ፤ በጣልያንና በኢትዮጵያ መካከል የደረሰውን ጠብ የሚዳኙት የራሴ ሰዎች ናቸው ብሎ ሲያቀርብ፤ የመንግሥታት ማህበር ዋና ጸሐፊ ሥርዓቱ ትክክል አይደለም ብሎ ለመናገር አልደፈረም። የዱቼን የንቀት ውሳኔ እንደአላየ አይቶ፤ የተሠየሙት ዳኞች ጥናታቸውን ቀጥለው፤ እስከ ነሐሴ 3 ቀን 1935 ዓ.ም ድረስ፤ ራፖራቸውን እንዲያቀርቡ ከማሳሰብ በስተቀር አንዳች አስተያየት መስጠት አልፈለገም።

መቸም በዚያን ጊዜ፤ የጉልበተኞች ሐሳብ የሚደመጥበት ዘመን ስለሆነ፤ የደካሞችና የድሆች አገሮች ውሳኔያቸውን አሜን ብለው ከመቀበል በስተቀር፤ ሌላ ምን ማድረግ ይችላሉ ?

# ምዕራፍ ፫

## የእንግሊዞች የዕርቅ ሐሳብ
### አንቶኒ ኤደን ከሙሶሊኒ ጋር

ከወልወል ግጭት በኋላ፤ በጣልያንና በኢትዮጵያ መካከል የተነሣው ጠብ እየከረረ በመሄድ ወደ ጦርነት የሚያመራ ከሆነ፤ በዤኔቭ በሚገኘው የመንግሥታት ማህበር እና እንዲሁም በዓለም ላይ ከፍ ያለ ጠንቅ ሊያስከትል ይችላል በማለት፤ የታላቋ ብሪታንያ ዋና መልዕክተኛ የሆነው አንቶኒ ኤደን ከፍ ያለ ሥጋት አድሮበት ነበር። ለዚህም፤ እስከተቻለው ድረስ የጣልያንና የኢትዮጵያ ጉዳይ አንድ ዓይነት የሰላም መፍትሔ እንዲገኝለትና የሊግ ኦፍ ኔሽንም ሕይወት ተጠናክሮ ለመኖር እንዲችል፤ ብዙ ጥረት ሲያደርግ እንደነበረ ታይቷል። ኤደን ያደረበት ሥጋት በሚከተሉት ሁኔታዎች ላይ የተመሠረቱ ነበሩ። እነዚህም፡-

1ኛ/ የፋሽስቱ መንግሥት መሪ ቤኒቶ ሙሶሊኒ የሚፈልገው፤ የወልወልን ግጭት መነሻ በማድረግ፤ ኢትዮጵያን በጦር ኃይል ለመውረርና ቅኝ ግዛቱ ለማድረግ መሆኑን ኤደን ተገንዝቧል።

2ኛ/ ኢትዮጵያ ከፋሽስት ጣልያን ጋር በምንም ምክንያት ጦርነት ለማንሣት የማታስብና፤ በመንግሥታት ማህበር ዳኝነት ዕምነት በማድረግ፤ ሰላምን አጥብቃ እንደምትፈልግ፤ አንቶኒ ኤደን ደህና አድርጐ ተመልክቷል።

3ኛ/ የአውሮፓ ታላላቅ መንግሥታት የሆኑት እንደ ታላቋ ብሪታንያና እንደ ፈረንሣይ የመሳሰሉት አገሮች፤ በዚያን ሰዓት ሙሶሊኒ ከሂትለር ጋር ተሰልፎ ሰላም እንዳይነሣቸው በመፍራት፤ በደል የሚፈጸምባትን ኢትዮጵያን ለመርዳት ጠቃሚ እርምጃ እንደማይወስዱ ኤደን በሚገባ ያውቃል።

4ኛ/ የመንግሥታት ማህበር አባል የሆነችውን ኢትዮጵያን የፋሽስት መንግሥት በጦር ሲወራት፤ የተጠቂዋን ነፃነት ለመከላከል ሊግ ኦፍ ኔሽን በግፈኛው መንግሥት ላይ እጅግ የጠነከረ እርምጃ መውሰድ ሲገባው፤ በታላላቆቹ የአውሮፓ አገሮች አቋም ምክንያት ምንም ለማድረግ እንደማይችል አንቶኒ ኤደን ተረድቶታል።

ስለዚህ፤ ምን ማድረግ ይሻላል ? .... አንቶኒ ኤደን ኢትዮጵያ አቅም የሌላት ድኃ አገር በመሆኗ፤ ከሕግ ውጭ በሚደርስባት ጥቃት እጅግ የሚያዝንላት ቢሆንም፤ የተወከለበትን መንግሥት ፖሊሲ ከመከተል በስተቀር፤ ለተበደለችው አገር ፊት ለፊት ጠበቃ ሆኖ ለመታገል የሚችልበት መንገድ አልነበረውም። እርግጥ ነው ! ከግንቦት 20 ቀን 1935 ዓ.ም ጀምሮ በተደረገው የኮንሰርቫቲፍ መንግሥት የካቢኔ ለውጥ፤ አንቶኒ ኤደን የሊግ ኦፍ ኔሽን ጉዳይ ሚኒስትር ተብሎ

ተሾሟል። ይሁን እንጂ፤ የሹመቱ የፕሮቶኮል ደረጃ ከፍ ቢልም፤ በተመደበበት ሥራ ላይ ቀድሞ ከነበረው ተጨማሪ ሥልጣን አልተሰጠውም። በግልጽ እንደታወቀው በዚያን ዘመን የታላቋ ብሪታንያ መንግሥትና ሕዝብ፤ በአገሮች መካከል ለሚፈጠር አለመግባባት ሁሉ፤ በሊግ ኦፍ ኔሽን ዳኝነት ላይ የሚያምንና የሚመረኮዝ ነው። ስለዚህም፤ ለአንቶኒ ኤደን ከካቢኔው የተሰጠው ኃላፊነትና የተጣለበት አደራ፤ የኢትዮጵያና የጣልያን ጉዳይ በመንግሥታት ማህበር አማካይነት የሰላም መፍትሔ እንዲገኝለት፤ ብርቱ ጥረት ከማድረግ በስተቀር በታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ስም አጥቂውንና ተጠቂውን በመለየት አቋም መውሰድ አያስፈልግም የሚል ነው።

ይሁን እንጂ፤ ሚስተር ኤደን የተሰጠውን ፖሊሲ የሚያከብር ቢሆንም፤ የሙሶሊኒ መንግሥት በዕብሪት መንፈስ ኢትዮጵያን ለመያዝ የሚያሳየውን ሁኔታ ለመቃወም መሞከሩ አልቀረም። ለምሳሌም ያህል አንድ ጊዜ፤ በሊግ ኦፍ ኔሽን ምክር ቤት ስብሰባ ላይ የሙሶሊኒ መልዕክተኛ፤ « እኛ እኮ ክብራችንን ለመጠበቅና የሚደረግብንን ጥቃት ለመመለስ የፈለግነውን ሁሉ ማድረግ እንችላለን » የሚል የማስፈራሪያ ቃል ሲወረውር፤ « ... እዚህ ሁላችንም የምንገኘው የመንግሥታት ማህበርን ሕግና ሥርዓት ለመከተልና ለማክበር ነው እንጂ፤ አግባብ የሌለውን ዛቻ ለማዳመጥ አይደለም ... » ብሎ መልስ የሰጠው፤ ከታላላቆቹ አገሮች መካከል አንቶኒ ኤደን ብቻ መሆኑን ያስተዋሉ መልዕክተኞች ነበሩ። በእውነትም በኢትዮጵያና በጣልያን ጉዳይ ወደ ለንደን በሚልካቸው ራፖሮች ውስጥ፤ የኢትዮጵያን መንግሥት ትክክለኛ አቋምና ሰላም ፈላጊነት እያስረዳ፤ የዱቼ ሙሶሊኒ ፍላጐትና ዓላማ የመንግሥታት ማህበርን መሠረት የሚያፈርስ መሆኑን እየደጋገመ ከማሳሰብ አላቋረጠም ነበር። « ... በእኔ አስተያየት ሲኞር ሙሶሊኒ ኢትዮጵያን በጦር ኃይል ለመያዝ የሚያደርገውን ሩጫ እቁሞ፤ ለችግሩ ሌላ መፍትሔ ከማግኘት በስተቀር፤ እሱ በግሉ የሚያስበውን ሁሉ መፈጸም እንደማይችል፤ ግልጽ በሆነ መንገድ አጥብቆ መንገር ያስፈልጋል ... » በማለት ለካቢኔው የገለጸው አስተያየት፤ የፋሽስት ግሥጋሴ አደገኛነቱ ለኢትዮጵያ ብቻ ሳይሆን፤ ለአውሮፓም ሰላም ክፉ ጠንቅ መሆኑን አንቶኒ ኤደን እንደሚያምንበት የሚያመለክት ነው።

የወልወል ግጭት ከደረሰ ከአምስት ወራት በኋላ፤ የጣልያንና የኢትዮጵያ ጉዳይ ወደ ሰላም እንዲያመራ ምንም ዓይነት መፍትሔ ስላልተገኘለት፤ አንቶኒ ኤደን አንድ "የዕርቅ ሐሳብ " ይዞ፤ እ.ኤ.አ ሰኔ 24 ቀን 1935 ዓ.ም ሮም በመገኘት ለዲክታተሩ መሪ ለቤኒቶ ሙሶሊኒ አቀረበ። ይህም በእንግሊዝ ኤክስፐርቶች ተጠንቶ፤ የስታንሌይ ባልድዊን (STANLEY BALDWIN) ካቢኔ የተስማማበት የዕርቅ ፕላን፤

1ኛ/ ኢትዮጵያ የኦጋዴንን አውራጃ በሙሉ ለጣልያን መንግሥት እንድትሰጥ፤

2ኛ/ የእንግሊዝ መንግሥት ደግሞ በብሪቲሽ ሱማሌላንድ በኩል ያለውን የዘይላን የወደብ በር ለኢትዮጵያ እንዲለቅ፤

3ኛ/ የጣልያን መንግሥት ከኢትዮጵያ ጋር የወዳጅነት ስምምነቱን በማደስ፤ በአገሪቱ ውስጥ ለኢኮኖሚ እድገት ምቹ የሆኑትን አንዳንዶቹን

አውራጃዎች ለማልማት እንዲችል፣ የታላቋ ብሪታንያን ትብብር እንደሚያገኝ፣

የሚገልጽ ሐሳብና ጥናት ነበር።

ኤደን ይህን ሐሳብ ይዞ ወደ ሮም የተጓዘው፣ ሙሶሊኒ፣ ኦጋዴንን የሚያህል ትልቅ ግዛት ሲያገኝ፣ ከዚህም በቀር በኢትዮጵያ አውራጃዎች ውስጥ የኢኮኖሚ ልማት እያስፋፋ ለመጠቀም የሚችልበት ዕድል ሲከፈትለት፣ የመንግሥታት ማህበርን ደንብ ጥሶ የኢትዮጵያን ነፃነት ለመግፈፍ የሚያደርገውን ዝግጅት ሊያቆም ይችል ይሆናል የሚል ተስፋ በማሳደር ነው።

እ.ኤ.አ ሰኔ 24 ቀን 1935 ዓ.ም በሮም የቬኒሲያ ቤተመንግሥት (PALAZZO-VENEZIA) በመገኘት፣ የታላቋ ብሪታንያ የሊግ ኦፍ ኔሽን ጉዳይ ሚኒስትር የዕርቁን ፕላን ለሲኞር ሙሶሊኒ ሲያቀርብ፣ የገለጻቸው ዋና ዋናዎቹ መሠረታዊ ሐሳቦች የሚከተሉት ነበሩ።

« ... የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት በጣልያንና በኢትዮጵያ መካከል የተፈጠረው አለመግባባት፣ በሰላም ጉዳና እንዲያልቅ ከልቡ ሲጨነቅና ሲያስብ የቆየ ነው። ይህም ሰላም እንዲገኝ አስፈላጊው ጥረት መደረግ ያለበት፣ ሁላችንም ግዴታ ገብተን በመሠረትነው በሊግ ኦፍ ኔሽን በኩል እንዲሆን የታላቋ ብሪታንያ መንግሥትና ሕዝብ ጥልቅ ምኞትና ዕምነት ነው። ይህንንም የሕዝብ ፍላጐትና ስሜት በመከተል፣ "ሊግ ኦፍ ኔሽን" የተቋቋመበትን ዓላማ ከግቡ ለማድረስ እንዲችል፣ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት የገባበትን ቃል ኪዳን በትክክል የሚፈጽም ከመሆኑም በላይ፣ የውጭ ጉዳይ ፖሊሲውንም የመሠረተው በዚሁ ማህበር ላይ ነው። ስለዚህም፣ የሊግ ኦፍ ኔሽንን ተግባር የሚፃረር፣ ወይም አቋሙን የሚያናጋ ችግር ቢፈጠር፣ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት በቸልታ የሚመለከተው ጉዳይ መሆን አይችልም።

... በአሁኑ ሰዓት በታላቋ ብሪታንያ ውስጥ፣ ሕዝቡም ሆነ አገሩን እንዲመራ የተመረጠው መንግሥት፣ በፓርላማውም ያሉት የደጋፊዎቹ ሆኑ የተቃዋሚዎቹ ወገኖች፣ ሁሉም በአንድነት በሊግ ኦፍ ኔሽን ዓላማና ግብ ከልባቸው የሚያምኑ ስለሆኑ፣ በመካከላችን አንዳች የሐሳብ ልዩነት አይገኝብንም። ... በመንግሥታት መካከል ችግር በተከሠተ ጊዜ ኃይልን ተመርኩዞ በጦርነት የሚገኝ መፍትሔ ሁሉ፣ ከዚህ ቀደም በሰው ልጆች ላይ ያደረሰው ጥፋት ምን ያህል እንደሚያሳዝን ሁላችንም በዕድሜያችን ደርሰን አይተነዋል። ዛሬም፣ ይህን የመሰለው አደጋ እንዳይደገም፣ ለጋራ ሰላምና ፀጥታ ጠባቂያችን እንዲሆን ያቋቋምነው የመንግሥታት ማህበራችን፣ ዓላማውን ይዞ ግቡን እንዲመታ ማድረግ፣ ከሌሎቹ ይበልጥ የእኛ የአውሮፓውያን ኃላፊነት ነው። በዚህም መሠረት፣ በጣልያንና በኢትዮጵያ መካከል የተፈጠረው ችግር፣ የታላቋ ብሪታንያን መንግሥት እጅግ አድርጐ ስለአሳሰበው፣ አንድ ዓይነት መፍትሔ የሚሆን ሐሳብ በማጥናት፣ እርዳታችንን ለመለገስ ወደ ሮም መጥተናል። ይህንንም የሰላም ጥረት ለማድረግ የምንደከመው፣ የተለየ ጥቅም ለማግኘት ወይም ለአፍሪካ ጉዳይ ብለን ሳይሆን፣ ፍጹም በሆነው አውሮፓዊነታችን፣ ግዳጃችንን ለመፈጸም ነው ... » ::

ካስ በኋላ፣ አንቶኒ ኤደን ቀደም ሲል የተገለጸውን የዕርቅ ፕላን ሲያቀርብ፣ ከዱቼ ሙሶሊኒ ጋር የተለዋወጧቸው አስተያየቶች የሚከተሉት ነበሩ።

ኢደን፤ ኢትዮጵያ ከግዛቶቿ ውስጥ የኦጋዴንን አውራጃ በሙሉ ለጣልያን እንድትሰጥና፤ በተጨማሪም በአገሪቱ ውስጥ የርስዎ መንግሥት ከፍ ያለ የልማት ሥራዎች እያከናወነ ለመጠቀም እንዲችል፤ ታላቋ ብሪታንያ አስፈላጊውን ድጋፍ ለመስጠት ዝግጁ ነች። ይህም ሐሳብ በሁለቱ አገሮቻችሁ መካከል በመልካም መንፈስ እንዲፈጸም፤ ታላቋ ብሪታንያ በሱማሌ ላንድ ግዛቷ በኩል፤ የዘይላን ወደብ ኢትዮጵያ እንድትጠቀምበት ለማድረግ ወስናለች። ይህንን የሰላም መፍትሔ እንዲሆን ያቀረብንልዎትን ሐሳብ የሚቀበሉት ከሆነ፤ ጣልያን ከኢትዮጵያ ላይ ትልቁን የኦጋዴንን ግዛት በምትረከብበት ጊዜ፤ ታላቋ ብሪታንያ ከመንግሥትዎ የምትጠይቀው እርዳታ፤ የብሪቲሽ ሱማሌላንድ ሕዝቦች ወደ ኦጋዴን ግዛት እየዘለቁ በልማድ እስከዛሬ የሚጠቀሙበት የግጦሽ ሣር፤ እንዳይቋረጥባቸው ብቻ ነው።

ሙሶሊኒ፤ ያቀረቡልኝን ሐሳብ በጥንቃቄ አዳምጫለሁ። ከሁሉ በፊት ታላቋ ብሪታንያ የዘይላን ወደብ ለኢትዮጵያ ስትለቅ፤ ብዙ ችግር የሚያስከትል ስለሆነ፤ በጥብቅ እንቃወማለን። የዚህም ዋናው ምክንያት፤ ኢትዮጵያ የባሕር በር ስታገኝ፤ የፈለገችውን የጦር መሣሪያ እያስገባች፤ ኃይሏን የበለጠ ለማጠናከር እንደሚያስችላት በትክክል ስለምናውቅ ነው። ...

ኢደን፤ እዚህ ላይ ላቋርጥዎትና ! የርስዎ ሥጋት የዘይላ ወደብ ለመሣሪያዎች ማስገቢያ ይሆናል የሚል ከሆነ፤ ይህንን ለማስወገድ የሚያስችል መንገድ እናገኝለታለን።

ሙሶሊኒ፤ ችግሩ እንደዚህ በቀላሉና ባጭሩ የሚፈታ አይደለም። ኢትዮጵያ፤ እናንተ ያሰባችሁላትን የባሕር በር ካገኘች፤ ጉልበት እየተሰማት በተለይ ከብዙ ዓመታት ጀምሮ በጥላቻ ዓይን ለምትመለከታት ለጣልያን እጅግ አስቸጋሪ ለመሆን ያስችላታል። ኢትዮጵያ እንኳንስ የባሕር በር አግኝታ፤ ሳይኖራትም በአሁኑ ሰዓት በምታደርገው በኮንትሮባንድ የመሣሪያ ንግድ፤ ለእኛም ለእናንተም በቅኝ ግዛቶቻችን በኩል ሰላም እንዳልሰጠች የታወቀ ነው። ስለዚህም፤ ይህ ያቀረቡት ሐሳብ፤ ኢትዮጵያ ከታላቋ ብሪታንያ ጋር ያላትን ወዳጅነት እጅግ ከፍ የሚያደርግና፤ ታላቋ ብሪታንያም የኢትዮጵያ ደጋፊና ጠበቃ መሆኗን የሚያመለክት ከመሆኑ በስተቀር፤ እኛን የሚጎዳ እንጂ፤ የሚጠቅም ነገር አላገኘንበትም።

ኢደን፤ በታላቋ ብሪታንያ መንግሥት በኩል ይህን የመሰለ አስተሳሰብ የለም። ያቀረብንልዎ ጥናት፤ በጣልያንና በኢትዮጵያ መካከል የተፈጠረው ችግር የሰላም መፍትሔ እንዲያገኝ ከልብ በማሰብ እንጂ፤ አንዱን ጎድቶ አንዱን ለመጥቀም አይደለም። ስለዚህ፤ ሐሳባችንን ሚዛናዊ በሆነ መንገድ እንዲመለከቱትና በእኛም ላይ ለሐቀኛነታችን ዕምነት እንዲጥሉብን እጠይቃለሁ።

ሙሶሊኒ፤ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ይህን ሐሳብ ያጠናው፤ ለሰላም በማሰብና ልባዊ በሆነ መንፈስ መሆኑን አልተጠራጠርኩም። ነገር ግን፤ ለመቀበል አልችልም ያልኩት፤ ይህ የዕርቅ ሐሳብ ለጣልያን ምንም

ጥቅም የማይሰጥና ይልቁንም ኢትዮጵያን የሚረዳ ሆኖ ስለአገኘሁት ነው።

ኢደን፣ ቀደም ብዬ እንደጠቀስኩልዎ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት፣ የራሱን ጥቅም አሳልፎ በመስጠት ያቀረበው ሐሳብ፣ በጣልያንና በኢትዮጵያ መካከል ሰላም ተገኝቶ የጦርነት አደጋ እንዲወገድ በመጨነቅ ስለሆነ፣ በዚህ ጉዳይ ላይ የተቀረጠ ውሳኔዎን በጥሞና አስበውበት፣ መልሱን ዛሬውኑ ሳይሆን ለምን በሌላ ጊዜ አይሰጡኝም ?

ሙሶሊኒ፣ በእኔ በኩል ያለኝ ሐሳብ የሚለወጥ ስላልሆነ፣ ሌላ ቀጠሮ ለማድረግ የሚያስፈልግ አይመስለኝም። ይሁን እንጂ፣ እርስዎ እዚህ ሮም ድረስ መጥተው የመንግሥትዎን ልባዊ የሆነ ስሜት ግልጽ በሆነ መንገድ ሲያስረዱኝ፣ እኔም በበኩሌ፣ ስለ ኢትዮጵያ ጉዳይ ያለኝን እውነተኛውንና የተቀረጠ ሐሳቤን ብነግርዎ የተገባ ይመስለኛል።

ኢደን፣ በጣም ደስ ይለኛል።

ሙሶሊኒ፣ እኔ ከኢትዮጵያ ጋር ያለ ጦርነት የሰላም ስምምነት ለማድረግ ዝግጁ የምሆነው፣

1ኛ/ ከጥንታዊው ዘመን ጀምሮ ኢትዮጵያ ነፃ መንግሥት እየተባለች የኖረችው አሁን ከያዘቻቸው ልዩ ልዩ አውራጃዎች ውስጥ፣ ጉንደርንና ትግሬን፣ ጉጃምንና ሸዋን በመያዝ ብቻ ስለሆነ፣ በዚሁ መሠረት በእነዚሁ ግዛቶች ላይ በጣልያን የበላይ ተቆጣጣሪነት የውስጥ አስተዳደር አቶኖሚ ተቀብላ ለመኖር እስማማለሁ ካለች፣

2ኛ/ ሌሎቹን ካለፉት አምሳ ዓመታት ጀምሮ እያቀናሁ ይዠቸዋለሁ የምትላቸውን በደቡብ ኢትዮጵያ የሚገኙትን ግዛቶች በሙሉ፣ ከሐረርና ከኦጋዴን አውራጃዎች ጋር ለጣልያን መንግሥት ለመልቀቅ ፈቃደኛ ከሆነች፣ እኔና የምመራው መንግሥቴ ከኢትዮጵያ ጋር የሰላም ስምምነት ለማድረግ ፈቃደኞች እንሆናለን። ነገር ግን፣ ኢትዮጵያ ይህን ለመቀበል ካልፈለገች፣ ለጣልያን ያላት ምርጫ ወደ ጦርነት ማምራት ይሆናል። ጦርነቱ የማይቀር ሆኖ ጣልያን ተዋግታ ድሉን ካገኘች በኋላ ደግሞ፣ የሚፈጠረው ሁኔታ የተለየ ይሆናል። ይኸውም፣ ኢትዮጵያ በሙሉ ትያዛለች ማለት ነው። ኢትዮጵያ በሙሉ ከተያዘች ደግሞ ከዓለም ጂዮግራፊ ካርታ ላይ ትደመሰሳለች ማለት ነው። ... እስካሁን ድረስ ጣልያን ወደ ኢትዮጵያ ወሰን አንድ መቶ ሃምሳ ሺህ ጦር ልካለች። ይህም በቂ ስላልሆነ የምንልከው ጦር እስከ አምስት መቶ ሺህ እንዲደርስ በመዘጋጀት ላይ ነን። ... በጣልያንና በኢትዮጵያ መካከል ከአድዋ ጀምሮ ለብዙ ዘመናት የኖረው ችግር በቶሎ መፈታት አለበት። አድዋ ላይ ምኒልክ ያሰለፉት ጦር ዘጠና ሺህ ሲሆን፣ ጣልያን የነበሯት ተዋጊዎች አሥራ አራት ሺህ ብቻ ነበሩ። ጣልያን የተሸነፈችውና በታሪኳ ላይ ውርደት የተቀበለችው፣ በዚህ አቻ በሌለው የጦር ዝግጅት

ማዕበል ውስጥ ወድቃ ነው። የጣልያን ሕዝብ ይህን ብድር ለመመለስና ታሪኩን ለማደስ የጠነከረ ስሜቱንና ፍላጐቱን አሳይቷል። ስለዚህም፣ ይህንን በሕዝባችን ላይ ያደረውን መንፈስ፣ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥትና ሕዝብ ሊገነዘቡለት ይገባል።

ኢደን፣ ቀደም ብለው እንደተናገሩት ስለ ኢትዮጵያ የሚያስቡትን ሁሉ እውነተኛውን ጉዳይ እንዳውቀው በግልጽ ስለነገሩኝ አመሰግንዎታለሁ። በበኩሌ አሁን በመጨረሻ ስለ አድዋ እንሥተው የገለጹት አስተያየት እጅግ አድርጐ ስለአሳዘነኝ፣ ጨርሶ የማልቀበለው መሆኑን እንዲረዱልኝ እፈልጋለሁ። በአለንበት ዘመን ማንም አገር የጥንት ታሪኩን እያገላበጠ ተዋግቶ ድል የሆነበትን አገር ሁሉ፣ ብድር ለመመለስ ለጦርነት የሚዘጋጅ የለም። በአሁኑ ሰዓት የማናችንም አገር በዚህ መንፈስ ለመመራት መብት የለውም። በተለይ ታላቋ ብሪታንያ ይህን ዓይነቱ ዕምነት ጨርሶ እንደሌላት በማያዳግም ሁኔታ ላረጋግጥልዎ እወዳለሁ። እስከ ዛሬ ድረስ ሊግ ኦፍ ኔሽንና የአውሮፓ ታላላቅ አገሮች በጣም ሲጨነቁበት የቆዩት፣ በጣልያንና በኢትዮጵያ መካከል ጠቡ የተነሣው በወልወል በደረሰው ግጭት ምክንያት ስለሆነ፣ ለዚህ እንዴት አንድ መፍትሔ አይገኝለትም ? በሚል ስሜት ነው። አሁን ከእርስዎ ንግግር እንደተረዳሁት፣ ይህን ሁሉ ጦር ወደ ኢትዮጵያ የሚልኩት፣ የአድዋን ቂም ለመበቀል ከሆነ፣ ሊግ ኦፍ ኔሽንና ታላቋ ብሪታንያ እንዲሁም ታላላቆቹ አገሮች፣ በጣልያን ላይ ያላቸውን አቋም መለወጥ ግዴታ ይሆንባቸዋል።

ሙሶሊኒ፣ የለም እንዲህ አይደለም። ሁለታችንም የምንወያይበት የፈረንሣዊኛ ቋንቋ የእናት ቋንቋችን ስላልሆነ፣ አንዳንዱን ጉዳይ ስንረዳ የተዛነፈ አስተያየት ሊገጥመን ይችላል። የአድዋን ጉዳይ ያነሣሁት፣ ታሪኩንና በጣልያን ሕዝብ ላይ ያሳደረውን ስሜት ለማስታወስ እንጂ፣ ዛሬ ከኢትዮጵያ ጋር የገጠመኝ ችግር መሠረቱ "አድዋ" አለመሆኑን እኔም አረጋግጥልዎታለሁ።

ኢደን፣ እርግጥ ነው ! እርስዎ እንዳሉት አንዳንድ ጊዜ ሁለት ሰዎች በሌላ ባዕድ ቋንቋ ሲወያዩ፣ በመሠረተ ሐሳቡ ላይ አንዳንድ አለመግባባት ሊገጥማቸው ይችላል። የርስዎ ፈረንሣዊኛ በስዊስ ቃና ላይ የተመሠረተ ጥሩ ፈረንሣዊኛ ነው። የእኔም ይህን ያህል መጥፎ አይመስለኝም። ያም ሆነ ይህ፣ በጣልያንና በኢትዮጵያ መካከል የተፈጠረው ጠብ በወልወልም ጉዳይ ሆነ ወይም በሌላ የቀድሞ ምክንያት፣ የእርስዎ መንግሥት ወደ ጦርነት እንዲያመራ የሚደግፍ የለም። ከጦርነት ለመዳንና ከኢትዮጵያ ጋር የሰላም ስምምነት ለማድረግ እንዲቻል፣ እርስዎ ያቀረቡትም መፍትሔ፣ ኢትዮጵያን ከዓለም ቤተሰብ ውስጥ እንደደሌለች አድርጐ የሚቆጥር ነው። በእኔ አስተያየት ከኢትዮጵያ ሕዝብ ውስጥ ይህን የርስዎን ሐሳብ የሚቀበል ከመቶ አንድ እንኳ ይኖራል አልልም። ንጉሠ ነገሥቱም፣ ምንም እንኳ ሰላምን ፈላጊነታቸው የታወቀ ቢሆንም፣ ይህን ሐሳብ ከመቀበል ጦርነትን የሚመርጡ ይመስለኛል። ከእኛ በኩል ያቀረብንልዎ የዕርቅ ሐሳብ፣ ምንም ዓይነት ተቀባይነት የሌለው ከሆነና፣ መንግሥትዎ

በኢትዮጵያ ላይ የኃይል እርምጃ ለመውሰድ ከወሰነ፣ በሁለቱ አገሮቻችን መካከል ባለው መልካም ግንኙነት ላይ የሚያደርሰውን ትልቅ ጉዳት በሥጋት መንፈስ እንደምመለከተው አልደብቅዎትም። እንደዚሁም፣ እርስዎ የሚወስዱት እርምጃ በሊግ ኦፍ ኔሽን ላይ ከባድ ችግር የሚፈጥር በመሆኑ፣ በታላቋ ብሪታንያ ሕዝብ ዘንድ የሚያስከትለውን ከፍ ያለ ቅሬታና ቁጣ በቀላሉ መመዘን አይቻልም። እንደሚያውቁት፣ የሊግ ኦፍ ኔሽን ጉዳይ የሚያስጨንቀው ታላቋ ብሪታንያን ብቻ አይደለም። ሌሎቹንም ታላላቅ መንግሥታት ጭምር ነው።

ሙሶሊኒ፣ ፈረንሣዮችን ለማለት ነው ?

ኢደን፣ አዎን ! ከእኛ ጋር የሊግ ኦፍ ኔሽን ጉዳይ ከሚያሳስባቸው አገሮች አንዷ ፈረንሣይ ነች። አሁን በቅርቡ፣ የፈረንሣይ ጠቅላይ ሚኒስትር በመሆን አዲሱ ካቢኔውን በማቋቋም ላይ የሚገኘው ወዳጁ ሙሴ ፒየር ላቫል፣ ወደ ሮም መምጣቴን ስነግረው፣ እሱም በበኩሉ የጣልያንና የኢትዮጵያ ጉዳይ እንደሚያሳስበው ለሲኞር ሙሶሊኒ ንገርልኝ ብሎኝ ነበር።

ሙሶሊኒ፣ (እጅግ በመገረም) ሙሴ ላቫል፣ ከስድስት ወራት በፊት ሮም መጥቶ በነበረ ጊዜ፣ በኢትዮጵያ ጉዳይ ጣልያን የምትፈልገውን ሁሉ ለማድረግ "ነፃ እጅ" (Main Libre) ያሳት መሆኗን አስታውቆን ነበር።

ኢደን፣ "በኢኮኖሚ መስክ ብቻ ነዋ ! "

ሙሶሊኒ፣ እርስዎ የሚጠቅሱት በጽሑፍ የተፈራረምናቸውን ሰነዶች ነው። እኛ ተነጋግረን የተስማማነው በኢኮኖሚም፣ በፖለቲካም መስክ፣ ጣልያን በኢትዮጵያ ላይ የፈለገችውን እንድታደርግ ነው።

ኢደን፣ ሙሴ ላቫል ከሮም ጉዞው በኋላ፣ ዡኔቭ በመጣ ጊዜ ከሲኞር ሙሶሊኒ ጋር የተስማማውን ለእኔ የነገረኝ፣ ጣልያን በኢትዮጵያ ውስጥ ለመሥራት የምትችለው በኢኮኖሚ መስክ ብቻ መሆኑን ነው።

ሙሶሊኒ፣ (ራሱን እየነቀነቀ በጣም በመገረም ስሜት፣ መልስ መስጠት አልፈለገም።)

ኢደን፣ እስቲ ወደ ዋናው ጉዳያችን እንደገና እንመለስና፣ ባቀረብነው የዕርቅ ፕላን፣ ጣልያን በኢኮኖሚ መስክ ከሚኖራት ከፍተኛ ጥቅም በላይ፣ የኢትዮጵያን ትልቁን የኦጋዴን ግዛት ማግኘቷን እንዴት በቀላሉ ገመቱት ?

ሙሶሊኒ፣ እኔ በአፍሪካ ውስጥ የሚገኙትን የበረሀ አውራጃዎች፣ አግበስባሽ ወይም አጠራቃሚ መሆን ስለማልፈልግ ነው።

ኤደን፤ እንግዲያውስ፤ አንድ መንግሥት የሊግ ኦፍ ኔሽንን የአባልነት መብት እየተጠቀመ በሰላም ለመኖር፤ የማህበሩን ሕግና ግዴታ ከማክበር በስተቀር ሌላ ምርጫ እንደሌለው መታወቅ አለበት።

ሙሶሊኒ፤ የሊግ ኦፍ ኔሽን አባል የሆነ አንድ መንግሥት፤ የማህበሩን ደንብ ለመከተል በአንድ ምክንያት ወይም በሌላ ካልቻለ፤ ምን እንዲያደርግ ይጠበቅበታል ?

ኤደን፤ ለቅቆ መውጣት ይኖርበታል።

ሙሶሊኒ፤ አዎን ! ጃፓንና ጀርመን ተራ በተራ ማህበሩን ለቅቀው ወጥተዋል። ጣልያን እንኳ እንደዚያ ያለ ሐሳብ የላትም። ለማናቸውም እንዲሁ ለምሳሌ ያህል፤ ጣልያን ከማህበሩ ልውጣ ብትል ? የሊግ ኦፍ ኔሽን ሕይወት ይዳከማል ? ወይስ በሌላ መንገድ የሚጠናከርበት ዕድል ይኖረዋል ?

ኤደን፤ እኔ እንደሚመስለኝ፤ በእርስዎ አስተያየት ምናልባት የሊግ ኦፍ ኔሽን ጠበቃና ረዳት የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ብቻ ሆና ትታይዎት ይሆናል። እንደዚህ የሚያስቡ ከሆኑ ስሕተት ነው። የሌሎቹም የአውሮፓ አገሮች ሁሉ ለሊግ ኦፍ ኔሽን ዓላማና መልካም ግብ ከልብ የሚጨነቁና ብዙ የሚሠሩ ናቸው። ለምሳሌ፤ የእርስዎ መንግሥት፤ እንደ ጃፓንና ጀርመን ማህበሩን ለመልቀቅ የሚያስብ አለመሆኑን መናገርዎ በጣም ደስ የሚያሰኝ ነው። ይህን የተሰማኝን ደስታ ሳላቀዘቅዝ፤ አንድ ልመና ላቀርብልዎ እፈልጋለሁ። የሁላችንም የሰላም አስተባባሪያችንና አነጋጋሪያችን የሆነው ሊግ ኦፍ ኔሽን፤ ያለ እንዳች እንቅፋት ዓላማውን ይዞ ለመጓዝ እንዲችል፤ አባል መንግሥት ከሆነችው ከኢትዮጵያ ጋር ለተፈጠረው ችግር መፍትሔ እንዲሆን ያቀረብንልዎትን የዕርቅ ሐሳብ፤ ለምን አይቀበሉትም ? ብዬ በድጋሚ እጠይቅዎታለሁ።

ሙሶሊኒ፤ መቸም እርስዎ እስከ ሮም ድረስ የመጡበት ዋና ጉዳይ በመሆኑ፤ ጥያቄውን እየደጋገሙ ማቅረብዎ ሊያስደንቅ አይችልም። በሌላ መንገድ ደግሞ፤ ምናልባትም ጥያቄው እየተደጋገመ የሚቀርብልኝ፤ የኔ ውሳኔ የተሻሻለ ወይም የተለወጠ ነገር እንዳለበት ለማወቅም ይሆናል። ያም ሆነ ይህ፤ በእኔ በኩል በአሁኑ ሰዓት የተለወጠ ወይም የተሻሻለ ነገር የለም። እኔ በግልጽ እንዲታወቅልኝ የምፈልገው፤ የሰላም መፍትሔ ተቃዋሚ አለመሆኔን ነው። ነገር ግን፤ የሚቀርብልኝን የሰላም መፍትሔ የምቀበለው፤ የአገሬን ጥቅም የሚጠብቅልኝ ሆኖ ሳገኘው ብቻ ነው። ... ቀደም ሲል እርስዎ ሲናገሩ፤ አንድ የሊግ ኦፍ ኔሽን አባል የሆነ መንግሥት፤ የማህበሩን ሕግ አልከተልም ካለ፤ ለቅቆ መውጣት ይኖርበታል ብለው ነበር። እንግዲያውስ ! ካለፉት አሥራ ሁለት ዓመታት ጀምሮ፤ ለሊግ ኦፍ ኔሽን የገባችበትን ግዴታ አልፈጽምም ብላ የምታስቸግረው ኢትዮጵያ፤ ለምን ፍርዱ አይሰጣትም? ... እዚህ ላይ የፕሮቶኮሉ ሹም ገብቶ፤ የፋሽስቱ መሪ ለአንቶኒ ኤደን ክብር የሚሰጠው የምሳ ግብዣ መዘጋጀቱን ሲያስታውቅ፤ ውይይቱ ቆሞ በማግሥቱ ለመቀጠል እንዲቻል የዱቼ መልካም ፈቃድ ሆነ።



አንቶኒ ኤደን የታላቋ ብሪታንያ፣ ለሊግ ኦፍ ኔሽን ጉዳይ
በካቢኔ ሚኒስትር ማዕረግ ዋና መልዕክተኛ፣

## ሰኔ 25 ቀን 1935 ዓ.ም

በተሰጠው ቀጠሮ ከጠዋቱ በአራት ሰዓት የታላቋ ብሪታንያ የሊግ ኦፍ ኔሽን ጉዳይ ሚኒስትር በቬኔሲያ ቤተመንግሥት በመገኘት፣ ከጠቅላይ ሚኒስትሩ ጋር ስለ ኢትዮጵያ ጉዳይ በዋዜማው የጀመረውን ንግግር ቀጠለ።

ኤደን፣ ስለ ጣልያንና ኢትዮጵያ ጉዳይ በትናንትናው ዕለት ያደረግነውን ውይይት ወደ ሎንደን በመላክ ለካቢኔው እንዲቀርብ አድርጌ ነበር። መልሱ ዛሬ ጠዋት ደረሰኝ። ያቀረብነውን የዕርቅ ሐሳብ እርስዎ ያልተቀበሉት ስለሆነ፣ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ጥልቅ ኃዘን ተሰምቶታል። የርስዎ መንግሥት በማናቸውም መልክ ኢትዮጵያን ለመያዝ ያለው ዕቅድ፣ በ1906 ዓ.ም በእንግሊዝ፣ በፈረንሣይና በጣልያን መካከል የተደረገውን ስምምነት የሚጥስ መሆኑን የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ያምናል። እንደሚያስታውሱት፣ ይህ የ1906 ዓ.ም ስምምነታችን፣ ሦስቱ መንግሥታት (እንግሊዝ፣ ፈረንሣይ፣ ጣልያን) የኢትዮጵያን ነፃነት ሳይነኩ፣ አገሪቱን በዞን ተከፋፍለው ኤኮኖሚውን ለማልማት ይችላሉ የሚል ነው። እርስዎ ግን አገሪቱን በሙሉ መያዝ ያስፈልገኛል ብለው ሲነሡ፣ የኢትዮጵያን ነፃነት የሚሰርዙና የሌሎቹንም አገሮች የኤኮኖሚ ልማት መብት የሚፃረሩ ሆነው ይገኛሉ። የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ትልቁ ሥጋት ከሌላው ሁሉ የኢትዮጵያ ነፃነት ጉዳይ ነው። የኢትዮጵያ ነፃነት ከተነካ ደግሞ፣ የሊግ ኦፍ ኔሽን ሕይወት የሚያበቃለት እንደሚሆን ማሰብ ይቻላል።

ሙሶሊኒ፣ በ1906 ዓ.ም በሦስቱ አገሮች የተደረገው ስምምነት በተግባር እንዳይገለጽ ትልቅ እንቅፋት ሆና የኖረችው ኢትዮጵያ ነች። በቅኝ ግዛቶቻችን ወሰን ላይ ኢትዮጵያ ወንበዴዎች እያሠለጠነች ዘወትር የምትጥልብን አደጋና በኮንትሪባንድ መሣሪያዎች እያስተላለፈች፣ የዜጐቻችንን ሰላም እየነሣች እንደምትኖር ሁላችሁም ታውቃላችሁ። ይኸ ጉዳይ፣ ከብዙ ዓመታት ጀምሮ የኖረ ሲሆን፣ አሁን ደግሞ ኢትዮጵያ የምታደርገውን ሁሉ አተኩሮ መመልከት ያስፈልጋል። በአሁኑ ሰዓት ኢትዮጵያ ከግማሽ ሚሊዮን በላይ የሆነ ጦር አዘጋጅታ ትገኛለች። በአውሮፓ ውስጥ አንድ ዓይነት ጦርነት ቢከፈት፣ ኢትዮጵያ በመጀመሪያ ጣልያንን እንደምትወጋ በቂ መረጃዎች አሉን። ኢትዮጵያ ጦሯን አንሥታ በምትወጋን ጊዜ፣ ለጣልያን እርዳታ የሚሰጥ ማንም አገር እንደማይኖር ስለምናውቅ፣ ራሳችንን ለመከላከል መዘጋጀት ያለብን እኛ ነን። ...

ኤደን፣ ይህ የሚሉት በትክክል የሚታመን ከሆነ፣ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ከኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ጋር በቀጥታ እንደሚነጋገርበት ላረጋግጥልዎ እወዳለሁ። በአሁኑ ሰዓት እኛ ባለን መረጃ ግን፣ ኢትዮጵያ ሳትዘጋጅ የጣልያን መንግሥት ጦርነት አንሥቶ ይወጋናል በማለት ብርቱ ሥጋት ያደረባቸው ንጉሠ ነገሥቱ ናቸው።

ሙሶሊኒ፤ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ጥንቁቅ እና የተማሩ ሰው መሆናቸውን እናውቃለን።* ነገር ግን፤ በዙሪያቸው ያሉት መሳፍንትና መኳንንት፤ የእሳቸውን ሐሳብ የሚከተሉ አይደሉም። የራሶቹና የመሳፍንቶቹ ዋና ዓላማ፤ ምክንያት እየፈለጉ ጦርነት ማድረግና መዋጋት ብቻ ነው። ሌላ የሚያስቡት ነገር ስለሌላቸው፤ ደስታቸውም መዝናኛቸውም ጦርነት ነው። ሕዝቡም ለጦርነት ለመሰለፍ ከመዘጋጀት በስተቀር፤ ሌላ ነገር እንዳይሠራ አድርገውታል። እንግዲህ ! ለዚህ ሁሉ መድኃኒቱ፤ ጣልያን በአቀደችውና በጀመረችው ሥራ እንድትገፋበት፤ የታላቋ ብሪታኒያ መንግሥት መስማማት ይኖርባታል። ጣልያን ባቀደችው መንገድ የሚገኘው መፍትሔ ለታላቋ ብሪታንያም ትልቅ ጥቅም እንደሚያስገኝ ብታውቁልኝ ጥሩ ነበር ... »

እንግዲህ ! ከዚህ በላይ በዝርዝር እንደታየው፤ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ሚኒስትር አንቶኒ ኤደን፤ ከሎንዶን ይዞት የመጣውን የዕርቅ ሐሳብ ሙሶሊኒ እንዲቀበለው፤ ያደረገው ጥረት ሁሉ አልተሳካም። ሆኖም፤ ዱቼ በኢትዮጵያ ጉዳይ ላይ ያለው የተቆረጠ ዓላማና ግብ ምን መሆኑን፤ ከአንደበቱ በቀጥታ ለመስማት ከቻሉት የውጭ አገር መንግሥታት ባለሥልጣኖች ውስጥ፤ አንቶኒ ኤደን የመጀመሪያው ሰው ሆኗል። ሲኞር ፉልቪዮ ሱቪች (FULVIO SUVICH) የሙሶሊኒ የውጭ ጉዳይ ም/ሚኒስትር፤ ዱቼ ከኤደን ጋር ሲነጋገር ተገኝቶ በያዘው ማስታወሻ ላይ እንደጠቀሰው፤ « ... መሪያችን (ዱቼ) ስለ ኢትዮጵያ ጉዳይ የሚያስበውን ሁሉ እንደዚህ አውጥቶ በግልጽ ሲናገር የሰማሁት ለመጀመሪያ ጊዜ ነው ... » ብሏል። (ላቫልና ሙሶሊኒ የተነጋገሩት ብቻቸውን ስለሆነ፤ ምስክር አልተገኘም)

ሙሶሊኒ ከታህሣሥ 1934 ዓ.ም ጀምሮ፤ በፕሮፓጋንዳው ዓለምን ሲያታልል የቆየው፤ « ... ኢትዮጵያ ወልወል በተባለው የሱማሊያ ግዛቴ ላይ ላደረሰችብኝ ጥቃት፤ አጸፋውን መመለስ አለብኝ ... » እያለ ነበር። ለመንግሥታት ማህበር ባቀረበውም ክስ ከወልወል ጉዳይ ውጭ ሌላ የጠቀሰው ታሪክ አልነበረም። እርግጥ ነው ! ሙሶሊኒ በአገሩ ውስጥ በየአደባባዩ ሕዝቡን እየሰበሰበ ሲሰብክ፤ ጣልያን አንድ ቀን የአድዋን ብድር በመመለስ ታሪኳን እንደምታድስና በብዙ መቶ ሺህ የሚቆጠሩትም ባለሞያዎቹ ልጆቿ፤ ወደ አፍሪካ ሄደው የልማት ሥራ በማካሄድ ምን ያህል ለመበልጸግ እንደሚችሉ፤ ከልቡ የሚያስበውን ሲናገር፤ ይህች በጥቅል "አፍሪካ" የሚላት አገር ኢትዮጵያ መሆኗን ለመረዳት የሚያስቸግር አልነበረም።

በዚህ አኳኋን፤ ቤኒቶ ሙሶሊኒ ከእንግሊዙ ሚኒስትር ጋር በተወያየባቸው ጉዳዮች ውስጥ፤ ኢትዮጵያን ለመውረር የሚያዘጋጀው ጦር እስከ አምስት መቶ ሺህ እንደሚደርስና፤ ያደረገውንም ውሳኔ በምንም ዓይነት እንደማይለውጠው በግልጽ የተናገረበት ምክንያት ለምን እንደሆነ ለማወቅ፤ የቅርብ ረዳቶቹ እርስ በርሳቸው ሐሳብ ሲለዋወጡበት ሰንብተው ነበር። አንዳንዶቹ፤ ዱቼ የሚያስበውን ሁሉ ሳይመዝን እንደዚህ የገላለጠው፤ ምናልባት ከጤና መቃወስ ይሆን ? በማለት ሲሠጉ፤ ሌሎቹ ደግሞ፤ ዱቼ ያለ ጥርጥር እንግሊዞች በኢትዮጵያ ጉዳይ በምንም ረገድ ሊስማሙኝ አይችሉም በማለት ተስፋ ስለቆረጠ፤ ያበጠው ይፈንዳ ብሎ ነው

---

* The emperor himself was a cautious and educated man but the rases were quite different. (Mussolini 25/06/1935)

ይላሉ። እንግዲህ! በዚያም ቢባል በዚህ፤ የኢትዮጵያን ነፃነት ለመግፈፍ የታጠቀው ፋሽስት፤ የመነሻው መሠረቱ ምን መሆኑን ለማወቅ ይህን ያህል የጠለቀ ምርምር የሚያስፈልገው አይመስልም። ይህንን በሚመለከት ጉዳይ፤ በበኩሌ ያጋጠመኝን አንድ ሁኔታ ባጭሩ ለመግለጽ እወዳለሁ።

በጣልያን አገር የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ልዩ መልዕክተኛና ባለሙሉ ሥልጣን አምባሳደር በሆንኩበት ዘመን፤ ለብዙ ጊዜ ጠቅላይ ሚኒስትርና የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር የነበረው፤ የማከብረው ወዳጄ አልዶ ሞሮ፤ በመጋቢት 12 ቀን 1977 ዓ.ም በሮማ ዩኒቨርስቲ አዳራሽ፤ ስለ ሐያኛው ክፍለ ዘመን የፖለቲካ ታሪክ፤ ኮንፈራንስ ይሰጣል ስለተባለ፤ እኔም በዚያን ሰዓት ምንም እንኳ በአስቸጋሪው የስደት ሕይወት ላይ ብገኝም፤ እንደ ምንም ቦታ አግኝቼ ንግግሩን ለማዳመጥ ችዬ ነበር።

ሞሮ፤ ስለ ፋሽስት ዘመን ታሪክ ሲናገር፤ እ.ኤ.አ ከ1935 ዓ.ም ጀምሮ፤ ሙሶሊኒ ከአውሮፓ አገሮች የመንግሥታት መሪዎች ውስጥ፤ እኔን ማን ይደፍረኛል ? የሚል ብርቱ የሆነ የዕብሪት መንፈስ ያደረበት ዘመን ነበር። ካለ በኋላ፤ « ... ከዚህም ዕብሪቱ የተነሣ ለዚህ እጅግ ደግና ሰላማዊ ለሆነው የጣልያን ሕዝብ ክፉውን የመከራ ሕይወት የቀየሰለት፤ በመጀመሪያ ኢትዮጵያን በግፍ ሲወርና ሕዝቡን በጭካኔ ሲያስጨፈጭፍ ነው። ... በኢትዮጵያ ላይ ያንን ሁሉ አሰቃቂ በደል ካደረሰ ከአራት ዓመታት በኋላ፤ የፋሽስቱ መሪ ከሂትለር ጋር ሆኖ፤ የጣልያንን ሕዝብ ወደ ሥቃይ ማዕበል አስከትቶ፤ በመጨረሻ ፍጻሜው ያላማረለት ከንቱ ሆኖ ቀረ ... » በማለት አልዶ ሞሮ እርጋታንና ጨዋነትን አቀላቅሎ በያዘ መንፈስ አስተያየቱን ሲሰጥ፤ በዚያን ሰዓት የተሰማኝን ደስታና እርካታ ባጭሩ ልገልጸው የምችል አልነበረም። ይህንንም ከዛሬ ሠላሳ ዓመታት በፊት የያዝኩትን ማስታወሻ ለመጥቀስ የተነሣሁት፤ ሙሶሊኒ ስለአገራችን ጉዳይ ከኤደን ጋር ሲነጋገር ያሳየውን የማን አለብኝና የዕብሪት መንፈስ በማዛመድ ነው። በኢትዮጵያ ላይ ከፍተኛውን የጦር ዝግጅት የማደርገው የአድዋን ብድር ለመመለስ ነው በማለት እንደዚያ የፎከረው፤ እንደዚሁም ኢትዮጵያን መያዝ የምፈልገው በከፊል ሳይሆን፤ መላውን አገር በቅኝ ግዛት ለማስተዳደር ነው እያለ እንደዚያ በድፍረት የተናገረው፤ በዕብሪትና በጥጋብ መንፈስ ለመሆኑ የተለየ ማስረጃ ሊቀርብለት አይችልም።

የእንግሊዙ ሚኒስትር፤ ምንም እንኳ ዲክታተሩ የሚያሳየውን ዕብሪት አጥብቆ የሚቃወምና ከዚህም በላይ የፋሽስትን አመራር ከልቡ የሚጠላ ቢሆንም፤ ይህን አስተያየቱን በአደባባይ አውጥቶ ለመናገርና ለማውገዝ አይችልም ነበር። ምክንያቱም፤ በዚያን ሰዓት የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ፖሊሲ፤ ሙሶሊኒ ወደ ሂትለር ወጥመድ ሮጦ እንዳይገባ፤ በዲፕሎማሲ እያስታመሙ፤ አንዳንድ ጊዜም የሚጠይቀውን እየፈጸሙ ማቆየት ነው የሚል ስለሆነ፤ አንቶኒ ኤደን ከዚህ መምሪያ ለመውጣት መንገድ አልነበረውም።

አንዳንድ ታሪክ ጸሐፊዎች፤ አንቶኒ ኤደን ሮም ድረስ ሔዶ ከዲክታተሩ ከሙሶሊኒ ጋር ያንን ያህል የታገለው፤ ለኢትዮጵያ ሲል ነው የሚል አስተያየት ይሰነዝራሉ። እርግጥ ነው ! የሰላም መፍትሔ በማቅረብ ከዱቼ ጋር የተሟገተው፤ ኢትዮጵያንና ጣልያንን ለማስማማት መሆኑ የሚካድ አይደለም። ይሁን እንጂ፤ የኤደን የሮም ሚሲዮን የመጀመሪያው ግቡ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥትና ሕዝብ እጅግ የሚያምንበትና የውጭ ፖሊሲውም የተመሠረተበት "ሊግ ኦፍ ኔሽን" በኢትዮጵያና በጣልያን ጠብ ምክንያት እንዳይፈርስ ለማዳን መሆኑ መታወቅ

አለበት። ይህንንም፤ ኤደን ራሱ በታሪክ ማስታወሻው ላይ ደህና አድርጐ ገልጾታል።* አንቶኒ ኤደን ወደ ሮም በተጓዘበት ጊዜ፤ ኢትዮጵያን ለመርዳት የሚቻለው፤ ሙሶሊኒ የሊግ ኦፍ ኔሽንን ሕግ አክብሮ ነፃነቷን ሳይነካ፤ በአገሪቱ ውስጥ አንዳንድ የግዛትና የኤኮኖሚ ጥቅም በማግኘት፤ የሰላም ስምምነት ሲፈራረም ነው ብሎ አምኖ ነበር። ይህንንም ሐሳብ ውጤት ላይ ለማድረስ፤ በሙሶሊኒ ትዕቢት ምክንያት ባለመቻሉ፤ በተለይ በፋሽስትና የፋሽስት ደጋፊዎች በሆኑት ጋዜጦች ላይ፤ "ባዶ እጁን የተመለሰ ያልተሳካለት ዲፕሎማት" እየተባለ ብዙ ዓይነት ትችት ሲደረግበት ከረመ።

እንግሊዛዊው ሚኒስትር፤ ምንም እንኳ ወደ ሮም ይዞት የሄደው የዕርቅ ሐሳብ ተቀባይ በማጣቱ ያሳዘነው ቢሆንም፤ ከሙሶሊኒ ጋር ሁለት ጊዜ ተገናኝቶ ባደረገው ውይይት፤ ኢትዮጵያን ለመውጋት ዲክታተሩ የሚያደርገው ዝግጅት ሁሉ ከሕግ ውጭ መሆኑንና ይህም ጉዳይ የመንግሥታት ማህበርን መሠረታዊ አቋም እንደሚያፋልስ በጥልቅ እንዲገነዘበው በሚገባ ከማስረዳት አልተቆጠበም። እንዲያውም፤ የተሰጠውን መምሪያ እየጣሰ፤ ሙሶሊኒ የቀረበለትን የሰላም መፍትሔ አልቀበልም በማለቱ፤ በታላቋ ብሪታንያና በጣልያን መንግሥታት መካከል ያለውን ግንኙነት፤ እጅግ አድርጐ እንደሚጐዳው በጠንከረ ስሜት አስጠንቅቆታል። በተጨማሪም፤ የዲክታተሩን መንፈስ በአንዳንድ አነጋገር እየቀሰቀሰ፤ ኢትዮጵያን ለመውጋት መወሰኑን ብቻ ሳይሆን፤ የሚያዘጋጀውም ጦር መጠኑ እስከምን ድረስ ብዙ እንደሆነ ሊያወጣጣው ችሏል። እንግዲህ፤ እንግሊዛዊው ወጣት ሚኒስትር ይህን ሁሉ ጉድ ከዲክታተሩ አንደበት ከሰማ በኋላ፤ ትልቁ ጥያቄ ምን እርምጃ ወሰደ ? የሚለው ነው። ምንስ ማድረግ ይችል ነበር ? መልሱን ዛሬ አናገኘውም።

REFERENCE:

A. COLLOQUIO DI S.E. IL CAPO DEL GOVERNO CON ANTHONY EDEN
FULVIO SUVICH SOTTO SEGRETARIO DI STATO
(RESERVATISSIMO 24 GIUGNO 1935)

B. ATTEGGIAMENTO BRITANICO
NEL CONFLITTO ITALO — ETIOPICO
MINISTERO DEGLI AFFARI ESTERI
N°. 236477 AFF. POL. III

C. CONCESSIONE DA PARTE DEL GOVERNO
BRITANICO DI UNO SBOCCO AL MARE
ALL' ETIOPIA
MINISTERO DELLE COLONIE
7 — 7 — 1935 — XIII

D. POMPEO ALOISI
CHEF DE LA DELEGATION ITALIENNE
A LA SOCIETE DES NATIONS
JOURNAL 1935 - 1936

E. ANTHONY EDEN
FACING THE DICTATOR
MEMORY (1962)

---

* ANTHONY EDEN FACING THE DICTATORS (1962)